# ምዕራፍ ፩

## የኢትዮጵያን ጦርነት ለማፋጠን፤ ዱቼ የጦር አዛዡን ለወጠ።

ሙሶሊኒ፤ ከሊግ ኦፍ ኔሽን ጋር ለገጠመው ችግር መፍትሔ የሚሆነው፤ ወደ ኢትዮጵያ የዘመተው ጦር በተቻለ ፍጥነት ድል አድርጐ አገሪቱን በሙሉ ሲይዝ ነው የሚል ዕምነት ስለአደረበት፤ የመጀመሪያው እርምጃ አዲስ የጦር አዛዥ መመደብ ሆነ። በዚህም መሠረት፤ **እ.ኤ.አ ኅዳር 16 ቀን 1935 ዓ.ም ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ ቦኖን ሽሮ፤ ማርሻል ፒየትሮ ባዶሊዮን ሾመ።**

ከዚህ በፊት በነበረው በምዕራፍ ፭ ላይ እንደተገለጸው፤ የፋሽስት ሠራዊት የመረብን ወሰን ጥሶ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱን እንዲጀምር ሙሶሊኒ ለዋናው አዛዥ ለጄኔራል ደ ቦኖ ትዕዛዝ በሰጠ ጊዜ፤ « ... **ለእርምጃህ ፈጣን፤ ለግብህ እርግጠኛ መሆን አለብህ ...** » በሚል መመሪያ አስጠንቅቆት እንደነበረ ይታወሳል። ጦርነቱ ከተጀመረ ከአንድ ወር በኋላ ዱቼ ውጤቱን ሲያየው፤ እንደጠበቀው ሆኖ ባለማግኘቱ፤ በአዛዡ በደ ቦኖ ላይ ከፍ ያለ ቅሬታ አደረበት። እጅግ በተሟላ መሣሪያ የተሰለፈው የፋሽስት ጦር፤ በአምስት ሳምንታት ውስጥ ከመረብ አለፍ ብሎ በሚገኘው በትግራይ ክፍለ ሀገር፤ አድዋንና እንትጮን፤ አዲግራትንና መቀሌን ብቻ መያዙ በቂ ሆኖ አላገኘውም። **ከኢትዮጵያ በኩል የተዘጋጀ የመከላከያ ኃይል በሌለበት ክፍለ ሀገር አራት ከተሞችን ለመያዝ፤ ጄኔራል ደ ቦኖ አምስት ሳምንታት ከፈጀበት፤ በመላ ኢትዮጵያ ተዋግቶ ድል ለማድረግ አምስት ዓመታት ያስፈልገዋል ማለት ነው ? የሚል ትችት እስከ መናገር ደርሶ ነበር።** ከዚህ በላይ ደግሞ፤ ኤሚሊዮ ደ ቦኖ መቀሌን ከያዘ በኋላ፤ ለቤኒቶ ሙሶሊኒ በላከው ቴሌግራም፤ « ... **ወደ ሌላው የኢትዮጵያ ግዛት የምናደርገው ዘመቻ፤ በተረጋገጡ መረጃዎች የተደገፈና በብርቱ ጥንቃቄ መከናወን ስላለበት ጊዜ ያስፈልገናል ...** » የሚል ሐሳብ በማቅረቡ፤ ዱቼን የበለጠ አበሳጨው። ወዲያውም፤ ለጦሩ ዋና አዛዥ የሽረቱን ዜና ከማብሠሩ በፊት፤ በታላቁ የፋሽስት ምክር ቤት (Le Grand Conseil Fasciste) አባል ለሆኑት ዋና ዋና ሰዎች በጄኔራል ደ ቦኖ ላይ የሚከተሉትን ምክንያቶች ደርድሮ፤ የመጨረሻ ውሳኔውን አስታወቃቸው።

1. **ጦርነቱን እንደጀመረ፤ አድዋንና አዲግራትን በእጁ ካደረገ በኋላ፤ ወዲያውኑ መቀሌን እንዲይዝ የሰጠሁትን መምሪያ ችላ ብሎ ሲያመነታ፤ ብዙ ቀናቶች በከንቱ አጠፋ።**

2. **መቀሌን ከያዘ በኋላ ደግሞ፤ ሳይውል ሳያድር "ጦሩን ወደ አላጌ እንድትመራ ይሁን " ብዬ የሰጠሁትን ትዕዛዝ ለመቀበል ፈቃደኛ ባለመሆኑ፤ አጥጋቢ ያልሆኑ ምክንያቶች እየሰጠ እስካሁን ቆየ።**

3. ከብዙ ወራት ጀምሮ ጦራችን በሚገባ ከተዘጋጀ በኋላ፤ ለደ ቦኖ ደጋግሜ ያስጠነቀቅኩት፤

ሀ/ የኢትዮጵያ መንግሥት የመከላከያ ኃይሉን ያላደራጀ ስለሆነ፤ ጦራችን በፍጥነት እየተጓዘ፤ መላ ኢትዮጵያን ለመያዝ ከዛሬው ሰዓት የተሻለ ዕድል አለመኖሩን፤

ለ/ በሊግ ኦፍ ኔሽን በኩል የሚደርስብንን ጉዳት ለመቋቋምና ለዘለቄታውም ችግራችንን ለማስወገድ የምንችለው፤ ጦራችን በተቻለ ፍጥነት ኢትዮጵያን በሙሉ ይዞ ሲገኝ መሆኑን፤

ሐ/ ወደ ኢትዮጵያ ያሰማራነው ጦር እርምጃውን ካላፋጠነና ድልን በቶሎ ካልተቀዳጀ፤ የዛሬ ዐርባ ዓመታት የደረሰብን የአድዋ ውርደት ሊደገም እንደሚችል፤ በሚገባ ዘርዝሬ ነግሬአለሁ። የተሟላም ጦር አሰናድቼ ሰጥቻለሁ። ያጣሁት መምሪያ ተቀባይና ፈጻሚ ነው። ስለዚህ፤ በዛሬው ዕለት (ኅዳር 16 ቀን 1935 ዓ.ም) ዤኔራል ፒየትሮ ባዶሊዮን ከማርሻል የክብር ማዕረግ ጋር በዤኔራል ኤሚሊዮ ደ ቦኖ ቦታ የጦራችን ዋና አዛዥ አድርጌ ሾሜዋለሁ። ... » ሲል፤ በይፋ መግለጫ ሰጠ።

ኤሚሊዮ ደ ቦኖ ባላሰበውና ባልጠበቀው ሰዓት፤ ከዲክታተሩ መሪው ይህን የመሰለው አስደንጋጭ ቴሌግራም ሲደርሰው፤ ለጊዜው እውነት ይሆን ወይ ? ብሎ ማመን ቢያቅተውም፤ ሊሆን አይችልም፤ በሚል ተስፋም ራሱን ማታለል አልሞከረም። ይህ አሳዛኝ እርምጃ ተወስዶበት ከመቀሌ በአሥመራ በኩል ሮም ከተመለሰ በኋላ፤ ለአንዳንድ የቅርብ ወዳጆቹ እንደገለጸው፤ « ... ይህች ኅዳር 16 ቀን 1935 ዓ.ም ከዱቼ የተላከችልኝ ቴሌግራም፤ በሕይወቴ የማልረሳት ትልቅ ጠባሳ የተወችልኝ ነች ... » ብሏል። ይህ ያልጠበቀው ሽረት፤ ከመጠን በላይ ስሜቱን ነክቶት ሳይረሳው ቢኖርም፤ ከዘጠኝ ዓመታት በኋላ ደግሞ፤ ጥር 11 ቀን 1944 ዓ.ም ዱቼ ሙሶሊኒ ኤሚሊዮ ደ ቦኖን ተቃዋሚዬ ሆኗል በማለት፤ በምን አኳኋን በሕይወቱ ላይ ፈርዶ ከዚህ ዓለም እንዳሰናበተው ሲታይ፤ ለሟቹ ሳይሆን ለቀሪው ምን ያህል የበለጠ አሳዛኝ እንደሆነ ታሪኩ ወደፊት ይቀርባል።

ኤሚሊዮ፤ ቤኒቶን በዕድሜ አሥራ ሰባት ዓመት ይበልጠዋል። ሁለቱ ሰዎች በሚገባ የተዋወቁትና የወዳጅነት ግንኙነት የጀመሩት፤ እ.ኤ.አ በ1919 ዓ.ም ከመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ በኋላ ነው። በጦርነቱ ዘመን፤ ሙሶሊኒ ምንም እንኳ በፖለቲካ በጥባጭነቱና በጋዜጠኛነቱ የታወቀ ቢሆንም፤ የዘመተው በአሥር አለቃ (Caporal) ማዕረግ ስለሆነ፤ በዚያን ሰዓት ለሜጀር ጀነራልነት ደረጃ የተቃረበውን ብሪጋድየር ደ ቦኖን የመተዋወቅ ዕድል አላገኘም። ከጦርነቱ ፍጻሜ በኋላ፤ ሙሶሊኒ የፋሽስትን ፓርቲ ሚላኖ ላይ በይፋ ሲያቋቁም፤ ከጦር ሠራዊቱ መካከል ደጋፊዎቹ ሆነው ከተመዘገቡት ከፍተኛ መኰንኖች አንዱ፤ ሜጀር ጀነራል ኤሚሊዮ ደ ቦኖ ነበር። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ የሁለቱ ሰዎች መግባባትና ግንኙነት እየጠነከረ ሲሄድ፤ ሁለት ጨርሶ የማይመሳሰሉ ሰዎች በምን አኳኋን ወዳጆች መሆን ቻሉ ? እየተባለ በብዙ ታዛቢዎች ዘንድ ይተች ነበር። በልማድ እንደሚታወቀው፤ አንዳንድ ጊዜ ሁለት በብዙ ረገድ የማይመሳሰሉትን ሰዎች የሚያቀራርባቸውና በወዳጅነት የሚያስተሳስራቸው እውነተኛው ምክንያት ምን

የዱቼ ሙሶሊኒ የጦር አለቆች፤ (ፎቶ ኢ.ጥ.ም.ተ)



ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ ቦኖ



ማርሻል ፒየትሮ ባዶሊዮ፤
(ሕዝባችንን በጋዝና በመርዝ የጨረሰ)



ማርሻል ሮዶልፎ ግራዚያኒ፤
(ሕዝባችንን በግፍና በጭካኔ ያስገደለ)

እንደሆነ ለማወቅ ስለማይቻል፣ የኤሚሊዮና የቤኒቶ ፍቅር ተአምር ነው ከማለት በስተቀር ሌላ ትርጉም አይገኝለትም።

እ.ኤ.አ በጥቅምት 1922 ዓ.ም የፋሽስት ሠራዊቱን አስልፎ ሥልጣን ለመንጠቅ ዱቼ ከሚላኖ ወደ ሮም ሲመጣ፣ ከዋና ዋና ረዳቶቹና የጉዞው አዘጋጆች ከሆኑት አንዱ፣ ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ ቦኖ ነበር። ሙሶሊኒ በሮማ በሕግ የተቋቋመውን የዴሞክራሲ መንግሥት ሥልጣን ነጥቆ የጣልያን መሪ ከሆነ በኋላ፣ ከ1922 ዓ.ም እስከ 1935 ዓ.ም ድረስ፣ በአሥራ ሦስቱ ዓመታት ውስጥ ደ ቦኖ፣ መጀመሪያ የፖሊስ ሠራዊት ዋና አዛዥ፣ ቀጥሎም የጣልያን ቅኝ ግዛት የነበረችው የሊቢያ ጠቅላይ ገዥ፣ ከዚያም የቅኝ ግዛቶች አስተዳደር የካቢኔ ሚኒስትር ሆኖ፣ ዲክታተሩን በታማኝነት ያገለገለ ሰው ነው።

እ.ኤ.አ በ1932 ዓ.ም ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ወግቶ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ በወሰነ ጊዜ፣ መጀመሪያ በኢትዮጵያ አካባቢ ያለውን ሁኔታ ጉብኝቶ እንዲያጠና፣ ቀጥሎም፣ ለወረራው አስፈላጊ የሆነውን ጦር በምሥጢር እንዲያዘጋጅ፣ ኃላፊነቱን የሰጠው ለጄኔራል ኤሚሊዮ ደ ቦኖ እንደነበረ ይታወሳል። በዚያን ጊዜ ወደ ኢትዮጵያ ለሚዘምተው ጦር፣ « ... ዕድሜህ ገፍቷል ካልተባልኩ በስተቀር፣ የአዛዥነቱ ክብር ለእኔ ቢሰጥ፣ ለአገልግሎቴ ታሪክ መደምደሚያ አክሊል ይሆነኝ ነበር ... » ሲል ልመናውን ያቀረበው ራሱ ደ ቦኖ ነበር። ሙሶሊኒም የተጠየቀውን ምንም ያህል ሳያመነታ ተቀብሎ ፈጸመለት።

ኤሚሊዮ ደ ቦኖ ከዚህ ቀደም በ1911 ዓ.ም ከቱርኮች ጋር፣ በ1916 ዓ.ም ከኦስትሪያ ጋር በተደረጉት ጦርነቶች የተዋጋና ብዙ ዝና ያተረፈ ወታደር ቢሆንም፣ ወደ ኢትዮጵያ የሚደረገውን ዘመቻ የተመለከተው ከባድና እጅግ አሳሳቢ አድርጐ ነው። በአድዋ ጊዜ ምንም እንኳ በውጊያው ተካፋይ የነበረ ወታደር ባይሆንም፣ አጥንቶ እንዳተረዳው፣ የኮሎኒያሊስት ጣልያን ሠራዊት ያንን ሁሉ ዘመናዊ መሣሪያ እንደተሸከመ፣ በምኒልክ ጦር የተዋረደውና የተሸነፈው፣ ኢትዮጵያውያኖች ከጥንት ጀምሮ ባላቸው የተዋጊነት ልምድና የጀግንነት ባሕርይ መሆኑን አምኖበታል።

ወዳጄ ክቡር ቢትወደድ አስፍሐ ወልደ ሚካኤል፣ በጠላት ዘመን ስለ አስተዳደር ጥናት ለማድረግ ከአሥመራ ወደ ሮም ተልከው በቅኝ ግዛት ጉዳይ ሚኒስቴር ውስጥ በቆዩበት ጊዜ፣ ስለ ጄኔራል ደ ቦኖ ከትክክለኛ ምንጭ ሲነገር የሰሙትን አጫውተውኝ ነበር። « ... ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመያዝ በወሰነ ጊዜ፣ ምሥጢሩን አካፍሎ የጦሩን ዝግጅት ኃላፊነት ለወዳጁ ለጄኔራል ደ ቦኖ ቢሰጠውም፣ በመጨረሻው የዘመቻው ዋና አዛዥ ሊያደርገው አላሰበም ነበር። ይህ ኃላፊነት ለእኔ እንዲሰጠኝ ብሎ ያመለከተው ደ ቦኖ ራሱ ስለሆነ፣ ዱቼ ወዳጁን ላለማስቀየም እምቢ ማለት አልቻለም። ወዲያውም ደ ቦኖ የጦሩ ዋና አዛዥ መሆኑ በይፋ ሲገለጽ፣ አንዳንድ ዋና ዋና የሆኑት ከፍተኛ የጦር መኰንኖች፣ ሰውየው በዕድሜው የገፋ ከመሆኑም በላይ (ሰባ ዓመት) በአሠራሩ ዝግ ያለ ስለሆነ ጥሩ ምርጫ አልተደረገም የሚል ትችት አሰምተው ነበር።

ሙሶሊኒና ደ ቦኖ የሚስማሙት፣ ጣልያን ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቷ ማድረግ ይገባታል በሚለው ዓላማ እንጂ፣ በዘመቻው አመራርና አገሪቱን በመያዝ ረገድ ተመሳሳይ የሆነ ሐሳብ አልነበራቸውም። በሙሶሊኒ በኩል የተደረገው ውሳኔ፣ ጦሩ

ከሚያስፈልግ በላይ እጅግ ተንዛዝቶ የተዘጋጀ ስለሆነ፤ ኢትዮጵያን በአጭር ጊዜ ውስጥ ለመያዝ ፈጣን እርምጃ ከመውሰድ በስተቀር፤ ጊዜ የሚፈጅ ፕላን ማውጠንጠን የአድዋን ታሪክ ማስደገም ይሆናል የሚል ነው። ደ ቦኖ ከዚህ የተለየ ሐሳብ የነበረው። የአድዋ ታሪክ ሊደገም ይችላል ብለን መሥጋት ያለብን፤ ከሁሉ አስቀድሞ የኢትዮጵያውያኖች የጦር አሰላለፍ፤ የመሪዎቻቸው አቋምና ለውጊያው ያቀዱት ዝግጅት እንዴት እንደሆነ ለማወቅ የሚያስችሉንን መረጃዎች በቅድሚያ ሳንጨብጥ የቀረን እንደሆነ ነው። የተረጋገጠ መረጃ ሳይኖረን፤ በጦር ኃይላችን ትልቅነትና በሠራዊታችን ብዛት፤ በከባድ መሣሪያዎቻችንና በአየር ኃይላችን በመመካት፤ ኢትዮጵያን በጥቂት ጊዜያት ውስጥ እጃችን እናስገባታለን ብለን መነሳት፤ አስተማማኝ አለመሆኑን ማሰብ አለብን። በልማድ እንደምናውቀው፤ በጦርነት ላይ ድል ሊቀና የሚችለው፤ መጀመሪያ በተገኙት ጠቃሚ መረጃዎችና ቀጥሎ ደግሞ በሚደረገው የውጊያ ስልት ነው። ከዐርባ ዓመታት በፊት አድዋም ላይ ጦራችን ድል የሆነው በመሣሪያዎች እጥረት ሳይሆን፤ ከጠላት ወገን በነበረው የውጊያ ስልት መሆኑን ለማመን ማፈር የለብንም። ዛሬም የምንደራጀው ይህንኑ አሳፋሪ የተባለውን ታሪክ በአዲስ ዝና ለመለወጥ ስለሆነ፤ ላለፈው አንጨነቅም። ይልቁንም ዛሬ ከተነሣንበት ዓላማና ከምንወስደው እርምጃ ጋር አብሮ መታሰብ ያለበት አንድ ሌላ ትልቅ ነገር መኖሩን ነው።

ኢትዮጵያውያኖች፤ አገራቸውን ለመያዝ የመጣንባቸው፤ ልናሠለጥናቸውና ከጨለማው ዓለም ወደ ብርሃን ልናሻግራቸው መሆኑን ደህና አድርገን ማስረዳት አለብን። ለዚህም ከዘማቹ ሠራዊታችን ጋር ጐን ለጐን እየተጓዘ የፕሮፓጋንዳውን ተግባር የሚፈጽም ድርጅት መቋቋም አለበት። ኢትዮጵያውያኖች ምንም እንኳ በአገር ፍቅር ጉዳይ ለመሥዋዕትነት ያላቸው ቆራጥነት የሚያጠራጥር ባይሆንም፤ አቀራረባችን የሚማርክ፤ አድራጐታችን ርኅራኄ የተመላበትና ክርስቲያናዊ መንፈስን የተከተለ ሆኖ ካገኙት፤ የመግባባት ዕድል ሊሰጡንና በሰላም ሊቀበሉን ይችላሉ። አለበለዚያ፤ በመሣሪያዎቻችን ኃይል ብቻ ተመርኩዘን፤ በግዴታ ተገዙልን ብለን፤ ከሰብዓዊ ተግባር ውጭ የምንጨክንባቸው ከሆነ፤ በቀላሉ ድል አድርገን ብንይዛቸውም፤ ለመቸውም ቢሆን ሰላም የሚሰጡን አለመሆናቸውንና እኛም ለምንጊዜውም አገራቸውን ይዘን በሰላም መኖር እንደማንችል ብናስብበት ይሻለናል። ስለዚህ፤ በተለይ አሁን አድዋን ይዘን፤ አዲግራትንና መቀሌንም በእጃችን ካስገባን በኋላ፤ ወደ ሌሎቹ የኢትዮጵያ ግዛቶች ለምናደርጋቸው ዘመቻዎች ሁሉ፤ በቅድሚያ የተረጋገጡ መረጃዎችን መሰብሰብና፤ በዚህም መሠረት ጦራችንን እያደላደልን ማሠማራት እንጂ፤ እንዲሁ በሚመስለን ወደ አላኄ አምባላጌ እንዝመት እያልን የችኮላ ውሳኔ ማድረግ የለብንም ሲል፤ ጄኔራል ደ ቦኖ ምሥጢራዊ ራፖሩን አቅርቦ ነበር። ይህ አስተያየት ሙሶሊኒን በጣም ስለአስቆጣ፤ የደ ቦኖ ሥልጣን በአጭሩ ተቀጨ። ቀድሞውንም ቢሆን፤ ለኢትዮጵያ ዘመቻ የደ ቦኖን አዛዥ መሆን፤ ከደጋፊው ተቃዋሚው የበዛበት ስለነበረ፤ ከተቀናቃኞቹ መካከል አንዱ የሆነውን ማርሻል ፒየትሮ ባዶሊዮን ለመሾም ሲኖር ዱቼ ጊዜ አልፈጀም።

ቢትወደድ አስፍሐ እንዳጫወቱኝ፤ ይህን ከዚህ በላይ የተገለጸውን፤ በሙሶሊኒና በደ ቦኖ መካከል የተፈጠረውን የሐሳብ ልዩነት የነገሩቸው፤ ቀደም ሲል የቅኝ ግዛቶች ጉዳይ ሚኒስቴርን ከሙሶሊኒ ቀጥሎ በዋና ዲሬክተርነት ይመራ የነበረውና ኋላም የኢትዮጵያ ገዥ የሆነው የዱካ ዳ አዖስታ (Duca Daosta) ምክትል ሆኖ የተሾመው፤ የታወቀው ፋሽስት ኤንሪኮ ቸሩሊ (Enrico Cherulli) ነው።

እንደሚታወሰው፤ አስፍሐ ወልደሚካኤል የቸሩሲ ካቢኔ ሹምና ዋና አማካሪ ሆነው የሠሩ ናቸው። ስለ ቢትወደድ አስፍሐ ወልደሚካኤል ከዚህ በላይ የቀረበውን የታሪክ ሂደት ለመጀመሪያ ጊዜ የሚያነቡ ሰዎች፤ ያለ ጥርጥር ሰውየውን የአገር ከሀዲ አድርገው ይመለከቷቸው ይሆናል። ነገር ግን አስፍሐ በጠላትም ዘመን ሆነ ከዚያም በኂላ ለሚወዷት ኢትዮጵያ ምን ያህል የተለየ አገልግሎት እንደአበረከቱ በኤርትራ ጉዳይ መጽሐፍ ውስጥ፤ ከገጽ 461 እስከ 469 ድረስ ባጭሩ የተገለጸውን ማንበብ እንደሚያስፈልግ ደራሲው በትሕትና ያሳስባል።

## አዲሱ የጦር አዛዥ

በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱ ከተጀመረ ከዐርባ ሦስት ቀናት በኂላ፤ በገኔራል ደ ቦኖ ቦታ አዲስ የተሾመው አዛዥ፤ ማርሻል ፒየትሮ ባዶሊዮ፤ (Mareshallo Pietro Badoglio) በዚያን ጊዜ የስድሳ አራት (64) ዓመት ዕድሜ የነበረው ሰው ነው። ባዶሊዮ፤ በውትድርና ትምህርት ያደገና ዘጠና በመቶ ዕድሜውን ያሳለፈው በውትድርና አገልግሎት ነው። የሐያ አምስት ዓመት ዕድሜ ከነበረው ዘመን ጀምሮ፤ መጀመሪያ በ1896 ዓ.ም አድዋ፤ ቀጥሎ በ1912 ዓ.ም ሊቢያ፤ ከዚያም በመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ዘመን በልዩ ልዩ የጦር ሜዳዎች ተካፋይ ሆኗል። በ1920 ዓ.ም የፋሽስት ፓርቲ በተመሠረተ ጊዜ፤ አባል አልሆንም በማለት የተቃዋሚነት አስተያየት ከሰጠ በኂላ፤ በ1922 ዓ.ም ሙሶሊኒ ሥልጣን ሲይዝ፤ በፋሽዝም አምናለሁ ብሎ በፓርቲው በመመዝገብ ዋና ደጋፊ ሆነ። ይሁን እንጂ፤ ሙሶሊኒ በዚህ ሰው ላይ ጥርጣሬ ስለነበረው፤ ለጊዜው ከጦር ሠራዊቱ ለማራቅ፤ በብራዚል የጣልያን አምባሳደር አድርጎ ላከው። በዚያን ጊዜ በጦሩ ክፍል የሜጀር ጀኔራል ማዕረግ የነበረው አምባሳደር ባዶሊዮ፤ በሪዮ ደዣነይሮ (Rio De Janeiro) በቆየበት በሁለቱ ዓመታት ውስጥ፤ ለፋሽስቱ መሪ ታማኝነቱን ለማሳየት ብዙ ጥረት ስለአደረገ፤ ወደ ሮም ተመልሶ በጦር ሠራዊቱ ውስጥ ከፍተኛ ቦታ ይዞ እንዲሠራ ተሾመ። ሙሶሊኒ ባዶሊዮን ማቅረብና በታማኝነቱ ላይ የነበረውን ጥርጣሬ ማስወገድ የቻለው፤ በዚህ በቺፍ ኦፍ ስታፍ መምሪያ ውስጥ በቆየበት በአምስቱ ዓመታት ውስጥ ባሳየው የኢንተሊጀንሲያ ሥራ ነው ይባላል።

በ1929 ዓ.ም ፒየትሮ ባዶሊዮ፤ ኤሚሊዮ ደ ቦኖን በመተካት የሊቢያ ጠቅላይ ገዥ ሆነ። ከስድስት ዓመታት በኂላ ደግሞ በደ ቦኖ ቦታ ለኢትዮጵያ ዘመቻ ዋና የጦር አዛዥ አድርጎ የሾመው፤ ዱቼ የሚፈልገውን ሁሉ በፍጥነት እንደሚፈጽምለትና እንደሚያስደስተው ከፍተኛ ዕምነት በማሳደር ነው። እንግዲህ ፤ ይህችን የፈረደባትን አገራችንን ቅኝ ግዛቱ አድርጎ ለመያዝ የዱቼ የተቀረጠ ውሳኔ ስለሆነ፤ ባዶሊዮ ጌታውን ለማስደሰት በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ ምን ያህል አሰቃቂ የሆነ የግፍ ሥራ እንደፈጸመ ታሪኩን ወደፊት እናያለን።

# ምዕራፍ ፲

## የኢትዮጵያ የጦር አለቆች አሰላለፍ

እ.ኤ.አ መስከረም 25 ቀን 1935 ዓ.ም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የ " ክተት አዋጅ " ካስነገሩ በኋላ፤ በሰሜን በኤርትራና፤ በደቡብ በሱማሌ በኩል፤ በሚገባ ተዘጋጅቶ የመጣውን የፋሽስት ጦር ለመከላከል፤ ዋና ዋናዎቹን አዝማቾች መርጠው እንደሚከተለው ደለደሉ።

ሀ/ ለሰሜን ጦር በሙሉ፤

ዋና ጠቅላይ አዝማች፡- ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ የበጌምድርና የሰላሌ ገዥ፤

1. በተንቤን ግንባር

| | |
|---|---|
| ዋና አዝማች፤ | ልዑል ራስ ሥዩም መንገሻ የትግራይ ገዥ፤ |
| በውስጣቸው | ደጃዝማች መሸሻ ወልዴ፤ የከምባታ ገዥ፤ |
| " | ደጃዝማች በየነ አባ ሰብስብ፤ የኮንታ ገዥ፤ |
| " | ደጃዝማች ወንድ ወሰን ካሣ፤ የበጌምድር እንደራሴ፤ |
| " | ደጃዝማች አበራ ካሣ፤ የሰላሌ እንደራሴ፤ |
| " | ደጃዝማች ኃይሉ ከበደ፤ የዋግና ሰቆጣ ገዥ፤ |
| " | ጸሐፊ ትዕዛዝ አፈወርቅ ወልደማርያም፤ የቀድሞ የጽሕፈት ሚኒስትር፤ |
| " | ደጃዝማች መንገሻ ይልማ፤ የጦር ሚኒስቴር ዲሬክተር፤ |
| " | ቀኛዝማች ደህኔ ወልደማርያም፤ የቀድሞ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር፤ |
| " | በጅሮንድ ለጥይበሉ ገብሬ፤ የቤተመንግሥቱ ዕቃ ቤት በጅሮንድ፤ |

2. በአላጌ ግንባር፤

| | |
|---|---|
| ዋና አዝማች፤ | ራስ ሙሉጌታ ይገዙ፤ የጦር ሚኒስትር፤ |
| በውስጣቸው፤ | ቢትወደድ መኮንን ደምሰው፤ የወሊጋ ገዥ፤ |
| " | ራስ ከበደ መንገሻ፤ የግድም ኤፍራታ ገዥ፤ |
| " | ራስ ጌታቸው አባተ፤ የከፋ ገዥ፤ |

" ደጃዝማች ወዳጆ ውቤ፤ የወሎ እንደራሴ፤

" ደጃዝማች ወልደማርያም በዳዳ፤ የገሙ ገዥ፤

" ደጃዝማች አውራሪስ ዱሉ፤ የመንዝ ገዥ፤

" ፊታውራሪ በየነ ሠራዊቱ፤ የወለኔን ጦር ይዘው፤

" ቀኛዝማች አበበ ረዴ፤ የማለፊያ ጠመንጃ ያዥን ጦር ይዘው፤

3. <u>በሸሬ ግንባር</u>

<u>ዋና አዝማች፤</u> ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ፤ የጐጃም ገዥ፤

በውስጣቸው፤ ደጃዝማች አያሌው ብሩ፤ የስሜን ገዥ፤

" ደጃዝማች መስፍን ገመች፤ የአገው ምድር አስተዳዳሪ፤

" ደጃዝማች አምባቸው ገሠሠ፤ የቀድሞ ሊቀመኳስ፤

" ደጃዝማች አበራ ተድላ፤ የማይጨው ገዥ፤

" ደጃዝማች አድማሱ ብሩ፤ የየጁ ገዥ፤

## <u>የደቡብ ጦር በሦስት ተከፈለ፤</u>

4. <u>ለቀኝ ደቡብ፤</u>

<u>ዋና አዝማች፤</u> ደጃዝማች ነሲቡ ዘአማኑኤል የሐረር እንደራሴ፤

በውስጣቸው፤ ደጃዝማች ሀብተሚካኤል ይናዱ፤ የኩሎ ገዥ፤

" ደጃዝማች መኮንን እንዳልካቸው፤ የይልባቦር ገዥ፤

" ደጃዝማች አበበ ዳምጠው፤ የጐፋ ገዥ፤

" ደጃዝማች አምደሚካኤል ሀብተሥላሴ የአሩሲን ጦር ይዘው

5. <u>ለግራ ደቡብ፤</u>

<u>ዋና አዝማች፤</u> ራስ ደስታ ዳምጠው፤ የሲዳሞ ገዥ፤

በውስጣቸው፤ ደጃዝማች ገብረማርያም ጋሪ፤ የአገር ግዛት ሚኒስትር

" ደጃዝማች መኮንን ወሰኔ፤ የወላይታ ገዥ፤

" ደጃዝማች ደባይ ወልደ አማኑኤል፤ በወለጋ ውስጥ የአውራጃ ገዥ፤

" ፊታውራሪ ታደሰ ገነሜ፤ የአውራጃ ገዥ፤

6. <u>ለማሕል ደቡብ፤</u>

## የቀ.ኃ.ሥ የጦር አዛዦች



ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ
አስተባባሪ ጠቅላይ አዝማች

ልዑል ራስ ሥዩም መንገሻ፤
በተንቤን ግንባር ዋና አዝማች



ክቡር ራስ ሙሉጌታ ይገዙ፤
በአላጌ ግንባር ዋና አዝማች

ክቡር ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ፤
በሽሬ ግንባር ዋና አዝማች

(ፎቶ ኢ.ጥ.ም.ተ)

| | |
|---|---|
| **ዋና አዝማች፤** | **ደጃዝማች በየነ መርዕድ፤ የባሌ ገዥ፤** |
| በውስጣቸው፤ | በጅሮንድ ፍቅረሥላሴ ከተማ፤ የገንዘብ ሚኒስትር፤ |
| " | ፊታውራሪ አጥናፍሰገድ ወልደጊዮርጊስ (የጉማይን ጦር ይዘው) |
| " | ቀኛዝማች አስፋው ወልደጊዮርጊስ፤ |
| " | ቀኛዝማች ሰለባና ቀኛዝማች አንዶም፤ (ከኤርትራ፣ ከጣልያን ከድተው የመጡ) |

እንግዲህ ! በሰሜን በኤርትራና በደቡብ በሱማሌ በኩል፤ በሰፊው ተዘጋጅቶ ከመጣው የጠላት ጦር ጋር እንዲዋጉ፤ ንጉሠ ነገሥቱ እየመረጡ በየግንባሩ የመደቧቸው የጦር አለቆች ከዚህ በላይ የተዘረዘሩት ሲሆኑ፤ እነዚህ አዝማቾች የተሰጣቸውን ኃላፊነት በምን አኳኋን እንደተቀበሉት ማተኮር ያስፈልጋል። ያለ ጥርጥር፤ ሁሉም ለኢትዮጵያ ነፃነትና ክብር መስዋዕትነት ከመቀበል ወደኋላ የሚሉ እንዳልሆኑ ማመን ይቻላል። ነገር ግን፤ ንጉሠ ነገሥቱ ባደረጉት የአዝማቾች ድልድል ላይ፤ አንዳንድ ቅሬታዎች መፈጠራቸውን መሸፈን አይቻልም። ለምሳሌም ያህል፤ ከብዙዎቹ ጥቂቶቹን መጥቀስ አስፈላጊ ይሆናል።

እ.ኢ.አቆ ጥቅምት 8 ቀን 1928 ዓ.ም፤ (18/10/35) ንጉሠ ነገሥቱ የኢትዮጵያን ጦር ሠራዊት ወደ ዘመቻ ባሰናበቱበት ሥነ በዓል ላይ፤ ታላቁን **ሰንደቅ ዓላማ ይዘው፤ « ... እኔ አሸክርህ ቀድሜ ሳልሞት፤ ጠላትህ ከፊትህ አይደርስም ... »** በሚል መፈክር <u>የጠቅላይ አዛዥነቱን ኃላፊነት የተቀበሉት፤ የጦር ሚኒስትሩ ራስ ሙሉጌታ ይገዙ መሆናቸው ይታወሳል።</u> በዚህ ዕለት ንጉሠ ነገሥቱም ለራስ ሙሉጌታ መፈክር በሰጡት መልስ፤ « ... **ላገርህ ነፃነትና ለኛ ለንጉሠ ነገሥትህ ክብር ደምህን ለማፍሰስ ቆርጠህ መነሳትህን ማየታችን ደስ አሰኝቶናል። ... አንተም ዕምነትህን በእግዚአብሔር ላይ አድርገህ የጦር ሠራዊታችንን እየጠበቅህ ለጠላት እንድትመክት አዘንሃል ...** » ብለው የተናገሩት ቃል፤ ለጠቅላላው የኢትዮጵያ ጦር አዛዥነት ከንጉሠ ነገሥቱ ቀጥሎ ከራስ ሙሉጌታ በስተቀር ሌላ ሰው ይኖራል የሚል ስሜት የሚያሳድር አልነበረም።

የጦር ሚኒስትሩ ታላቁን የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ ተረክበው ሠራዊቱን እየመሩ ጉዞአቸውን ወደ ትልቁ የሰሜን ግንባር ከቀጠሉ በኋላ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባወጡት አዲስ መምሪያ፤ **ለሰሜን ጦር በሙሉ ራስ ካሣ ኃይሉን ዋና ጠቅላይ አዝማች አድርገው መሾማቸው በይፋ ሲገለጽ፤ ራስ ሙሉጌታን እጅግ ያሳዘነ መሆኑ በሰፊው ተወራ።**

የምኒልክ የገንዘብ ሚኒስትር፤ የዘውዲቱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፤ ከዚያም የአባ መቻል የጌታ ፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ የሠላሣ ዓመታት የጦር አበጋዝነት ሥልጣን ሲፈጸም፤ የመጀመሪያው የጦር ሚኒስትር የሆኑት፤ ቀጥሎም ከራስ ብሩ ወልደ ገብርኤል ሽረት በኋላ፤ ለሁለተኛ ጊዜ ተፈልገው የጦር ሚኒስትርነቱ ሥልጣን የተሰጣቸው **ሙሉጌታ ይገዙ፤** ምንም እንኳ ለታወቁት መሥፍን ለልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ አክብሮት ያላቸው ቢሆንም፤ የጠቅላይ የጦር አዛዥነቱ ሥልጣን ሲወሰድባቸው፤ ቅር ቢሰኙ አያስገርምም።

እንደዚሁም፤ በደቡብ በኩል የተደለደሉት የጦር አዝማቾች ሁሉም ደስተኞች አልነበሩም። በተለይም ለግራ ደቡብ ዋና አዛዥ እንዲሆኑ የተመረጡት

## የደቡብ ጦር በሦስት ተከፈለ



ክቡር ራስ ደስታ ዳምጠው
ለግራ ደቡብ ዋና አዝማች፤



ክቡር ደጃዝማች ነሲቡ ዘ-አማኔል
ለቀኝ ደቡብ ዋና አዝማች፤



ክቡር ደጃዝማች በየነ መርዕድ
ለማሕል ደቡብ ዋና አዝማች፤

የሲዳሞ ገዥ ራስ ደስታ ሲሆኑ፤ በውስጣቸው ከተመደቡት ረዳቶች መካከል የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ደጃዝማች ገብረማርያም ጋሪ እንዲሆኑ በመደረጉ ፕሮቶኮል አልተጠበቀም ብለው የተቹ ብዙዎች ናቸው። በሌላ በኩል ደግሞ፤ ለቀኝ ደቡብ ዋና አዝማችነት ፕሮቶኮልን ለመጠበቅ ሲባል የተመረጡት የሐረሩ መስፍን እንደራሴ ደጃዝማች ነሲቡ ዘአማኑኤል ሲሆኑ፤ በውስጣቸው የተደለደሉትን የጦር ዕልቅና የብዙ ዘመን ልምድ ያላቸውን እንደ እነ ደጃዝማች አበበ ዳምጠው (ኋላ ሜጀር ጄኔራል) የመሳሰሉትን ቅር አሰኝቷል። በእነዚህ በታላላቆቹና በሌሎቹም አለቃና ጭፍራ ሆነው በተመደቡት መካከል፤ ይህን የመሳሰለው ቅሬታ መኖሩን ንጉሠ ነገሥቱ ደህና አድርገው ቢያውቁም፤ ኢትዮጵያ የመጣባትን ጠላት ለመከላከልና ነፃነቷን ለማዳን እያንዳንዱ ሰው የበኩሉን ግዳጅ መፈጸም እንጂ፤ የየግሉን ጉዳትና ጥቅም ማሰብ የለበትም የሚል አቋም በመያዝ ያደረጉትን ውሳኔ ማሻሻል አልፈለጉም። በዚህ አኳኋን፤ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አመራር በጦር አዝማቾች አመዳደብ ረገድ ከተፈጠረው ችግር ሌላ፤ በዚያን ዘመን በየአውራጃው ያሉት መኳንንቶችና ባላባቶች ከነተከታዮቻቸው፤ በተፈሪ መኰንን ላይ ያሳደሩት ቅሬታና ያላቸው አስተያየት ምን እንደነበረ መመልከት ያስፈልጋል።

ሀ/ የበጌምድርና የስሜን ታላላቆች፤ በንጉሥ ወልደጊዮርጊስ ቦታ ንጉሥ እንዳይሾም ከማገዳቸው በላይ፤ ባላባታችን የሆኑትን ራስ ጉግሣ ወሌን ገድለውብናል በማለት ተቀያሚዎች ሆነዋል።

ለ/ ጐጃሜዎች በጌታችን በንጉሥ ተክለሃይማኖት ቦታ ልጃቸው እንዳይነግሡ ከማድረጋቸው በላይ፤ የታወቁት የጐጃም መሳፍንቶች በአገሩ ላይ እያሉ፤ ከሸዋ የአክስታቸው የልጅ ልጅ የሆኑትን ራስ እምሩን ሾመው ልከውብናል በማለት ቅር ተሰኝተዋል።

ሐ/ ወሎዬዎች፤ በልጅ ኢያሱ ላይ የተፈጸመው ሁሉ ትክክል አልነበረም በማለት ከማዘናቸውም በላይ፤ ከኢማም አሊ አባ ቡላ ሲያያዝ የመጣው የራስ ሚካኤል አሊ ቤተሰብ ለወሎ ተጠሪ እንዳይሆን አጥፍተውታል በማለት ቂም ይዘውባቸዋል።

መ/ በሸዋ፤ የምኒልክ ምርቶች የሆኑት ሁሉ፤ ጣልያን የልብ ልብ አግኝቶ ነፃነታችንን ለመቀማት ጦር ይዞ የደፈረን፤ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ከፈረንጆች ጋር ከንቱ የሆነ የወዳጅነት ግንኙነት በመዘርጋት፤ የአገራችንን ገበና ለጠላት በማጋለጣቸው ምክንያት ነው በማለት፤ ጥፋተኛ ያደርጓቸዋል። ከእነሱም ጋር የሃይማኖት አባቶች የሆኑት ሁሉ፤ የንጉሠ ነገሥቱ አመራር ከፈረንጆች ጋራ እጅግ የተጣበቀ በመሆኑ፤ አገራችን የምታጣው ነፃነቷን ብቻ ሳይሆን ሃይማኖቷንም ጭምር ነው በማለት አውግዘዋቸዋል።

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ እንደታየው፤ የየአውራጃው መኳንንትና ባላባት፤ በአገሪቱ ላይ የመጣውን ጠላት በጠነከረ ሕብረት ለመውጋት በመሰለፍ ፋንታ፤ የንጉሠ ነገሥቱ የውስጥ አስተዳደር በድሎናል የሚባለውን ከአገር ጉዳይ ማስቀደማቸው፤ በዓለም ታሪክ ለነፃነቱ የማይበገር ሙት ነው ተብሎ ከፍተኛ ዝና የተሰጠውን የኢትዮጵያን ሕዝብ ክብር የሚያቃልል መሆኑን አልተረዱትም። በጐንደር ሆነ በጐጃም፤ በወሎ ሆነ በትግራይ፤ እንደዚሁም በሌሎቹ አውራጃዎች ነገሥታትን

ማንገሥና የገባር ጭቆናን አስተዳደር ወደነበረበት መመለስ፤ ኢትዮጵያ ከፌዎዳሉ ዓለም ሳትላቀቅ በስቃይ እንድትኖር መፍረድ መሆኑን መኳንንትና ባላባት ሲገነዘቡት አልቻሉም። የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አስተዳደር፤ ምንም እንኳ ትክክለኛ ፍትሕን ሙሉ በሙሉ በተግባር የሚያውል እንከን የሌለበት ነው ባይባልም፤ ዋና ዓላማው የኢትዮጵያን ሕዝብ ወደ ዘመናዊ ሥልጣኔ ለማሸጋገር ጥረት የሚያደርግ መሆኑን መገንዘብ የተገባ በሆነ ነበር። ነገር ግን፤ ተፈሪ መኰንን አልታደሉም። ለአገር ዕድገትና ለሕዝብ ብልፅግና ይጠቅማል ብለው የሚዘረጉትን ዕቅድ ሁሉ የፌዎዳሉቹ ወገኖች የተለየ ትርጉም በመስጠት ዕንቅፋቱን ስለአበዙባቸው፤ ሌላው ቀርቶ በዚያ በክፉ ቀን የአገሪቱን ነፃነት ከውጭ ጠላት ለመከላከል እንኳን፤ ሙሉ በሙሉ የሕዝቡን አንድነት ለማግኘት ሳይችሉ ቀርተዋል። ጠላት በመጣበት በልዩ ልዩ ግንባር እንዲዋጉ የሾሚቸውም የጦር አዝማቾች፤ የአንዱ ሥልጣን ከአንዱ መብለጥ፤ ወይም የአንዱ ከሌላው ማነስ ምክንያት እየሆነ፤ የሚጠበቅባቸውን የጀግንነት ተግባር በትክክል ለመፈጸም ያልቻሉ ነበሩ። ከዚህ ሁሉ በላይ ደግሞ ንጉሠ ነገሥቱ፤ ገና ከአልጋ ወራሽነታቸው ጀምሮ ሲተማመኑበት የኖሩት ሊግ ኦፍ ኔሽን፤ በግፈኛው ወራሪ ጠላት ላይ ያወጀው የኤኮኖሚ ዕገዳ ቅጣት፤ የሙሶሊኒን መንግሥት አዳክሞ፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር የሚያስችል አልሆነላቸውም። እንደዚሁም ኢትዮጵያን ከፌዎዳሉ ዓለም ለማላቀቅ በሚያደርጉት ጥረት፤ ደጋፊዎቼ ናቸው ብለው ተስፋ የጣሉባቸው የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት፤ ለነፃነት መከላከያ የሚያስፈልጓቸውን መሣሪያዎች፤ እንኳንስ በእርዳታ ሊሰጧቸው ይቅርና፤ በገንዘባቸው እንኳን ለመግዛት እንዲችሉ አልፈቀዱላቸውም። በዚህ ሁሉ ሁኔታ፤ ይህች የፈረደባት ኢትዮጵያ ነፃነቷን ገፍፎ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ የመጣባትን ጠላት ለመከላከል፤ በአገር ውስጥም ሆነ በውጭው ዓለም የሚያስፈልጋቸውን ድጋፍ ባለማግኘታቸው፤ ንጉሠ ነገሥቱ ምን ያህል የመረረ ሀዘንና ብስጭት ላይ እንደወደቁ መገመት ይቻላል።

ይሁን እንጂ፤ ተፈሪ መኰንን በተፈጥሮአቸው፤ የውስጥ ስሜታቸውን የማይገልጡና ለመከራ ደካማነትን ማሳየት የማይፈልጉ በመሆናቸው፤ ምንም ነገር እንዳልደረሰባቸው በማስመሰል፤ ባላቸው የመከላከያ ኃይል እስከሚቻላቸው ለመዋጋት እርምጃቸውን ቀጠሉ። ለመላው የኢትዮጵያ ሕዝብ ባስነገሩትም አዋጅ፤ « ... **ንጉሥ ወይም ጳጳስ ቢሞት ሰው ስለሆነ፤ ወዲያው ይተካበታል። የአገር ነፃነት ሲጠፋ ግን፤ ለዘለዓለሙ ባርነትን በሕዝብ ላይ ጥሎ የሚኖር ነው። ስለዚህ፤ ነፃነታችንን ቀምቶ ባሪያ አድርጐ ሊገዛን የመጣብንን ጠላት ለመመከት፤ ለኢትዮጵያ ሞትን ብትነፍጋትና ደምህን ሳታፈስላት ብትቀር፤ በፈጣሪህ የምትወቀስበት፤ በዘርህ የምትረገምበት ስለሆነ፤ ከጥንት የወረስከውን ጀግንነትህን ሳታበርድ ወደፊት የሚቆይህንም ታሪክ እያሰብክ፤ ጠላትን ለመውጋት ቆርጠህ ተነሣ። እኔም አብሬህ እሰለፋለሁ** ... » ሲሉ አሳሰቡ።*

---

* ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ

# ምዕራፍ ፤

## ከዘመቻው በፊት፤
## የልጅ ኢያሱ ፍጻሜ

ልጅ ኢያሱ ከተሻሩበት ከመስከረም 1909 ዓ.ም ጀምሮ በሐረርና በወሎ፣ በመቅደላና በአዳል በረሃ እየተዘዋወሩ እስከ ሚያዝያ 1913 ዓ.ም ድረስ፤ ለሃምሳ አምስት ወራት ከተፈሪ መኰንን እና ከአባ መቻል ሀብተጊዮርጊስ ጦር ጋር ሲዋጉ እንደኖሩ ይታወሳል።

በዚያ በውጊያው ዘመን አባ ጤና ኢያሱ አንድ ቀን ድል ይቀናቸውና አያታቸው ያወረሷቸውን ዘውድ መልሰው ይይዙ ይሆናል እየተባለ ስለሚፈራ፤ በሸዋ መኳንንት የተወሰነው የዘውዲቱ ምኒልክ ንግሥትነትና የተፈሪ መኰንን ባለሙሉ ሥልጣን አልጋወራሽነት ዋስትና ያለው ሆኖ አልተገመተም ነበር። ዕድሜ ለትግራዩ መስፍን ለራስ ጉግሣ አርዓያ፤ ልጅ ኢያሱ የራስ ሥዩምን ቤት ለቅቀው ከተሸሸጉበት ‹‹ስለዋ-ቅብፅያ›› ከተባለው ገዳም በሚያዝያ 1913 ዓ.ም በተያዙ ጊዜ፣ ለንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ምኒልክና ለቤተሰቦቻቸው አንድ ትልቅ ዕፎይታ ሆነ። ይሁን እንጂ፤ እስቸጋሪው ኢያሱ ከተያዙ በኋላ፤ ስለሚዘጋጅላቸው የእስር ቤት ሕይወት፣ ንግሥቲቱና አልጋወራሽ ተፈሪ ተመሳሳይ ሐሳብ አልነበራቸውም።

ንግሥቲቱ የታላቅ እህታቸው ልጅ ኢያሱ ሚካኤል፤ ባደረሱት ጥፋት ታድነው መታሰራቸው ትክክል መሆኑን ቢያምኑበትም፤ እግራቸው በሰንሰለት ተጠፍሮ በዚያ ብርዳም በሆነ ገጠር አፋፍ ላይ (በቡልጋ ወረዳ) ተዘግቶባቸው እንዲኖሩ መደረጉ፤ እጅግ አሳዘናቸው። ስለዚህም፤ ‹‹ .... **ጌታዬ ኢያሱ እዚህ አደጋ ላይ የወደቀው በዕድሜው ማነስና በእጉል ሰዎች ምክር ስለሆነ፤ እዚሁ አባቱ ዳግማዊ ምኒልክ ቤተመንግሥት ግቢ ውስጥ የተለየ ቤት ተሠርቶለት፤ አገልጋይና የታመኑ ጠባቂዎች ተመድበውለት የእስራቱን ዘመን ቢፈጽም ይሻላል** .... ›› የሚል ሐሳብ እስከማቅረብ ደርሰው ነበር። አልጋወራሽ ራስ ተፈሪና የጦር ሚኒስትሩ ፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ ይህንን የንግሥቲቱን ሐሳብ ጨርሶ የሚቀበሉት አልሆነም። የእነሱ አስተያየት፤ ‹‹ ..... **ልጅ ኢያሱ በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ ትልቅ ጥፋት የፈጸሙ ናቸው። አያታቸው ዳግማዊ አፄ ምኒልክ የጣሉባቸውን አደራ አልጠብቅም ብለው በጫሩት እሳት፤ ስንቱ መኳንንት፣ ስንቱ ጀግና፣ ስንቱ ሰላማዊ ሕዝብ አለአግባብ ደሙ ፈሰሷል ? .... እንደ ደንቡ ቢሆን ወንጀለኛውን ለፍርድ አቅርቦ የሞት ቅጣት ማስፈረድ ይቻል ነበር። ነገር ግን ታላቁ ጌታችንን ዳግማዊ አፄ ምኒልክን በማሰብ፤ ምንም ዓይነት የቅጣት ፍርድ ሳይወሰንባቸው በእስር ቤት ተጠብቀው እንዲቆዩ አድርገናል** .... ›› የሚል ነበር።

በዚህ ጉዳይ ታላላቆቹ የምኒልክ ሚኒስትሮችና ሊቀ ጳጳሱ ጭምር በተካፈሉበት ሰፊ ምክክር ከተደረገ በኋላ፤ ልጅ ኢያሱ ለንግሥቲቱም ሆነ ለአልጋወራሹ ታማኝ በሆኑትና እጅግ በተከበሩት በራስ ካሣ ኃይሉ የሰላሌና

የበጌምድር ገዥ እጅ ታስረው እንዲቆዩ ተወሰነ። ዘውዲቱ ምኒልክም፣ እጅግ ሲያስጨንቃቸው የነበረው የልጅ ኢያሱ የእስር ቤት ሕይወት፣ በራስ ካሣ እጅ እንዲሆን መደረጉ በጣም ስለአረካቸው የሰላም እንቅልፍ አገኙ። ይህ በተወሰነ በጥቂት ጊዜ ውስጥ በሰላሌ አውራጃ በፍቼ ከተማ በራስ ካሣ ግቢ ውስጥ በአስቸኳይ ልዩ የማረፊያ አዲስ ቤት ተሠርቶ እስረኛው ኢያሱ ከተዛወሩ በኋላ፣ በፊት ከከረሙበት ከቡልጋ ኮረማሽ ወረዳ ፤ በጣም የተሻለና የተመቸ ሕይወት በማግኘታቸው እጅግ ተደሰቱ። ከዚህ ከአዲሱ መኖሪያቸው እንደደረሱ፣ ‹‹ ጠላቶቼ በምግብ ውስጥ መርዝ ነስንሰው ሊገድሉኝ ይችላሉ ብዬ ስለምሠጋ፣ በአንቺ በእህቴ ላይ ሙሉ ዕምነት አለኝ ›› ሲሉ የራስ ካሣን ባለቤት ወይዘሮ ጽጌ በሻህን አጥብቀው ለመኗቸው። በዚህ መሠረት ከ1913 ዓ.ም እስከ 1924 ዓ.ም ድረስ ለዐሥራ አንድ ዓመታት በራስ ካሣ ግቢ ውስጥ ታስረው በቆዩበት ዘመን፣ በጾሙም ሆነ በፍስኩ ወራት ልጅ ኢያሱ የሚመገቡትን እየተቆጣጠሩ የሚያሠሩላቸው፣ ራሳቸው ወይዘሮ ጽጌ በሻህ (ኋላ ልዕልት) ነበሩ።

በራስ ካሣ ግቢ ውስጥ በተለይ ለልጅ ኢያሱ መኖሪያ አንድ ፎቅ ቤት የተሠራ ሲሆን፣ መግቢያውም ሆነ መውጫው በቤተመንግሥቱ እልፍኝ ላይ ስለሆነ፣ ለጥበቃ በጣም የተመቸ ነበር። በምድር ቤቱ ውስጥ አንድ ትልቅ ሳሎንና መታጠቢያ ቤት ያለው ሲሆን፣ በፎቁ ላይ አንድ ሰፊ መኝታ ቤትና ፀሐይ የሚሞቁበት በረንዳ ነበረው። በዚህ ራስ ካሣ በተለይ ባሠሩላቸው ቤት ውስጥ ከዐሥር ዓመታት በላይ በኖሩበት ዘመን፣ እስረኛው ኢያሱ ከቤት ወጥተው በከተማው ውስጥ ሆነ ከዚያም አልፈው ወደ ባላገሩ ዘልቀው ለመንሸርሸር መከልከላቸው ነው እንጂ፣ በሌላው ሕይወት በኩል አክስታቸው ንግሥት ዘውዲቱ እንደፈለጉት አንዳች ነገር አልተጓደለባቸውም። ከዚህም በቀር፣ ጠዋት ማታ ሳይለዩ እንዲያገለግሏቸው ከተመደቡላቸው ሰዎችና፣ በተለይም ከራስ ካሣ ዋና ዋና አሽከሮች ጋር እንደልባቸው መነጋገር ይችሉ ነበር። ከዚህ በላይ ደግሞ አልፎ አልፎ እጅግ የታመኑ ናቸው የተባሉና የታወቁ ሰዎች እንዲጐበኟቸው ሲፈቀድ፣ በሚስትነት ካገቧቸውም ሴቶች መካከል ከየጁ ባላባት የሚወለዱት ወይዘሮ ጥሩወርቅ አሊ ጋዝ አንዳንድ ጊዜ እየመጡ አብረዋቸው ይከርሙ እንደነበረ ታውቋል።

እንግዲህ ! ይህን የመሳሰለውን ነፃነት በማግኘታቸው፣ ልጅ ኢያሱ በሥልጣን በነበሩበት ዘመን ልጃቸውን ወይዘሮ ሰብለወንጌል ኃይሉን በማግባት አማታቸው ሆነው ከነበሩት ከጐጃሙ መስፍን ከራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት ጋር ግንኙነት ለመፍጠርና፣ ከዚህ ከታሰሩበት ከፍቼ ከተማ ለማምለጥ ስለሚችሉበት ጉዳይ ለመሳላክ የሚያስችል ዕድል አገኙ። በዚህ በልጅ ኢያሱና በራስ ኃይሉ መካከል ለሚደረገው ግንኙነት፣ ከራስ ካሣ ታማኝ አሽከሮች መካከል፣ የመኝታ ቤታቸው ኃላፊ አቶ ወይአንተ ኃይሉና የማዕድ (ምግብ) አቅራቢያቸው አቶ ቶጩ የተባሉት ሁለት ሰዎች ተባባሪዎች ሆኑ።

በተፈሪ መኰንን ላይ ምንጊዜም ተቀዋሚነታቸው ሳያቋርጥ የኖረው የጐጃሙ ገዥ ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት፣ በጥቅምት ወር 1923 ዓ.ም ለተከበረው የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የንግሥ በዓል ተካፋይ ለመሆን አዲስ አበባ ከመጡ በኋላ፣ ባልታወቀ ምክንያት ወደ ግዛታቸው ሳይመለሱ እንዲቆዩ ታዘው ስለነበረ፣ ከልጅ ኢያሱ ጋር በልዩ ኮድ መልዕክት ለመለዋወጥ የተመቸ ሆነላቸው። ልጅ ኢያሱ ከታሰሩበት ከፍቼ አምልጠው ቢወጡ፣ ደጋፊዎቻቸውን የወሎንና የጐጃምን፣

የጐንደርንና የትግሬን ሕዝብ አስነሥተው፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ለመጣልና የአያታቸውን የምኒልክን መንግሥት መልሰው ለመያዝ ይችላሉ የሚል ዕምነት ስለአደረባቸው፤ ራስ ኃይሉ ምኞታቸውን በተግባር ለማዋል ብርቱ ጥረት ማድረጋቸውን ቀጠሉ። በጣም ሀብታምና ባለ ገንዘብ በመሆናቸውም ሐሳባቸውን እንደግፋለን የሚሏቸውና የሚያበረታቷቸው አላጡም።

በአገር ውስጥ ካሉት የጣልያን ቆንስሎች ጋር ባላቸው ልዩ ግንኙነት፤ ልጅ ኢያሱ ወደ ሥልጣን ከተመለሱ በኢትዮጵያ ላይ ከፍ ያለ ጥቅም ታገኛላችሁ በማለት ዕቅዳቸውን ለማስፈጸም የሚያስችል እርዳታ እንዲደረግላቸው በምሥጢር ጠየቁ። ጣልያኖቹም ልጅ ኢያሱ ወደ ሥልጣን ከተመለሱ፤ ምናልባት እያታለልናቸው ኢትዮጵያን በሞግዚትነት የማስተዳደር ዕድል ይኖረናል በሚል ተስፋ፤ የራስ ኃይሉን ጥያቄ መደገፍና መርዳት የሚጠቅም መስሎ ታያቸው። በዚህም መሠረት፤ ልጅ ኢያሱ ከፍቼ አምልጠው ከወጡ በኋላ፤ በየክፍለ ሀገሩ ያለውን ሕዝብ ለማነሣሣት የሚዘዋወሩበት አንድ በማናቸውም ሜዳ ላይ በቀላሉ ማረፍ የሚችል አውሮፕላን፤ ጣልያኖቹ በልዩ ዘዴ ከአሥመራ እንደሚልኩላቸው ለራስ ኃይሉ ነገሯቸው። ይህ አውሮፕላን ከኤርትራ ከመነሣቱ በፊት በኢትዮጵያ ውስጥ በልዩ ልዩ አውራጃዎች እየበረረ ጉብኝት ለማድረግ እንዲችል፤ አዲስ አበባ ያለው የጣልያን ለጋሲዮን ፈቃዱን ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ካስወጣለት በኋላ፤ በሚያዝያ 1 ቀን 1924 ዓ.ም ከአሥመራ እስከ አዲስ አበባ አካባቢ በርሮ ሱሉልታ ሜዳ አረፈ። በዚህ ጊዜ ራስ ኃይሉ ያቀዱት ፕላን፤ እስረኛው ከፍቼ አምልጠው ሜጫ ላይ መድረሳቸውን እንደሰሙ፤ በሱሉልታ ሜዳ በተጠንቀቅ በሚጠብቃቸው በዚህ አውሮፕላን ተሳፍረው ወደተባለው ቦታ (ሜጫ) ለመሄድና ከዚያም ልጅ ኢያሱን ይዘው በጐጃምና በወሎ፤ በጐንደርና በትግራይ እየተዘዋወሩ፤ የምኒልክን የልጅ ልጅ ሕዝቡ በንጉሠ ነገሥትነት እንዲቀበላቸው ለማድረግ ነበር። ነገር ግን፤ በዚህ በሚያዝያ ወር ሁለተኛ ሳምንት ላይ ይፈጸማል ተብሎ በተጠበቀው ጊዜ፤ ልጅ ኢያሱ ከፍቼ ሳያመልጡ በመቆየታቸውና ከዚህም በላይ ያሉበት ሁኔታ ምን እንደሆነ ሳይታወቅ የአንድ ወር ጊዜ ስለአለፈ፤ የአውሮፕላኑ አዛዥ ባሮን ፍራንኬቲ (BARON FRANCHETTI) የታቀደው አልተሣካም ብሎ ተስፋ በመቁረጥ፤ ግንቦት 8 ቀን 1924 ዓ.ም አውሮፕላኑን አስነሥቶ ወደመጣበት ወደ አሥመራ ተመለሰ።* ይህ በሆነ በአምስተኛው ቀን፤ የራስ ኃይሉ ግብረአበሮች ልጅ ኢያሱን እንደ ሴት አልብሰው፤ የራስ ካሣ ባለቤት ወይዘሮ ጽጌ በሻህ ዘወትር እንደሚያደርጉት ወደ ቤተክርስቲያን እንደሚሄዱ በማስመሰልና አጀቡን በማሳመር፤ ማንም ሳይጠረጥር እስረኛውን ወደ ቀጠሮው ቦታ ወደ ሜጫ ለማሻገር ቻሉ። የጣልያን አውሮፕላን ከተመለሰ በኋላ፤ የልጅ ኢያሱ ማምለጥ ለራስ ኃይሉ እጅግ የሚያሳስብ ከባድ ችግር ሆነባቸው። ይህም ችግር ሊፈጠር የቻለው በሁለት በኩል በተደረገ ስሕተት መሆኑ ታወቀ። የመጀመሪያው፤ የራስ ካሣ አሽከሮች በቀጠሮው ጊዜ እስረኛው እንዲያመልጡ ለማድረግ አለመቻላቸውን ራስ ኃይሉ እንዲያውቁት መልዕክት ባለማስተላለፋቸው ሲሆን፤ ሁለተኛው ስሕተት ደግሞ፤ አውሮፕላኑ ወደ አሥመራ ለመመለስ ከሱሉልታ በተነሣ ጊዜ የእስረኛው ማምለጥ እንዲዘገይ፤ ራስ ኃይሉ ለግብረ አበሮቻቸው ባለማስታወቃቸው ነው።

ልጅ ኢያሱ ከፍቼ አምልጠው ሜጫ ላይ መድረሳቸውን በመግለጽ የጻፉት

---

* ቀ.ኃ.ሥ ሕይወቴና የኢት. እርምጃ ምዕራፍ 31

ደብዳቤ ራስ ኃይሉ ሲደርሳቸው፤ በአውሮፐላኑ መመለስ ምክንያት ያቀዱት ፕላን ሁሉ ስለተፋለሰ፤ ከእንግዲህ ወዲያ ምንም ነገር ለማድረግ እንደማይችሉ ተረዱት። በዚህም ጊዜ ልጅ ኢያሱን ባዶ ሜዳ ላይ ጥለው ራሳቸውን ለማዳን ስለፈለጉ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ዘንድ ቀርበው « **ከፍቼ አምልጬ ሜጫ ደርሻለሁ** » የሚለውን የአባ ጤናን ደብዳቤ በማሳየት፤ በደረሰው ሁኔታ እሳቸው የሌሉበት መሆናቸውንና ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴም ያላቸውን ታማኝነት ገለጹ። ንጉሠ ነገሥቱም ከብዙ ዘመን ጀምሮ በራስ ኃይሉ ላይ ምንም ዓይነት ዕምነት ስለሌላቸው፤ ጥርጣሬያቸውን በማጠንከር ከዚህ ዕለት ጀምሮ፤ ከቤተመንግሥት ካልተጠሩ በስተቀር ከቤታቸው ሳይንቀሳቀሱ በራቸውን ዘግተው እንዲቀመጡ ጥብቅ ትዕዛዝ ሰጡ። ወዲያውም የልጅ ኢያሱ ከፍቼ ማምለጥ ሲረጋገጥ፤ በተጠረጠሩት ሰዎች በራስ ኃይሉና በራስ ካሣ አሽከሮች ላይ ምርመራው ቀጠለ። ብዙ ጊዜ ሳይወስድ፤ የራስ ካሣ አሽከሮች አቶ ወይአንተና አቶ ፋጤ፣ እስረኛውን እንዲያመልጡ ያደረጉት እነሱ መሆናቸውን እውነተኛውን ሁኔታ አውጥተው ሲናገሩ፤ አዲስ አበባ በራስ ኃይሉም መኖሪያ ቤት በተደረገው ምርመራ፤ በኮሮጆአቸው (በርሳ) ውስጥ ከልጅ ኢያሱ ጋር በኮድ የተላላኩባቸው ሰነዶች ተገኙ። ከዚህ በኋላ፤ ራስ ኃይሉ ለንጉሠ ነገሥቱ በላኩት ማመልከቻ፤ « .... **ይህን ሁሉ ያደረግኩት ሰይጣን አሳስቶኝ ስለሆነ፤ በደግነትዎ ምሕረት ያድርጉልኝ** .... » ሲሉ ልመና አቀረቡ።

ልጅ ኢያሱ ከፍቼ ካመለጡ በኋላ፤ ቀጠሮ በተደረገበት በግንደበረትና በሜጫ እየተዘዋወሩ፤ ራስ ኃይሉ ከነገ ዛሬ ይደርሱልኛል በማለት ሲጠባበቁ፤ ሰውየው አዲስ አበባ ተይዘው ከቤት እንዳይወጡ መደረጉን ሰሙ። በዚህ ጊዜ ኢያሱ አባ ጤና፤ የተቻላቸውን ያህል ሙከራ ለማድረግ፤ ወደ ጐጃም ጉዞ ጀመሩ። ከአዲስ አበባም እስረኛው በራስ ኃይሉ ምክንያት ይደበቃሉ ተብሎ የተጠረጠረው ጐጃም ውስጥ ስለሆነ፤ የራስ ካሣ ልጅ ደጃዝማች አበራ ካሣ ከዋና ዋና ሰዎች ጋር ሆነው ልጅ ኢያሱን ለመያዝ ወደ ጐጃም ዘመቱ።

የልጅ ኢያሱ ከፍቼ ማምለጥ በአዲስ አበባ ከፍ ያለ ድንጋጤ ስለፈጠረ፤ በመላዋ ኢትዮጵያ ያሉት አገረገዦች ሁሉ እስረኛውን አድነው እንዲይዙ ከንጉሠ ነገሥቱ ጥብቅ ትዕዛዝ ተሰጥቷቸው ነበር። ይሁን እንጂ፤ እስረኛው ኢያሱ አባጤና፤ ዐባይን ተሻግረው ደብረማርቆስ ለመድረስ የሁለት ቀን መንገድ ሲቀራቸው፤ ፊታውራሪ ገሠሠ በለው የተባሉ የታወቁ የአገሩ ተወላጅ፣ እጃቸውን ይዘው፤ ለንጉሠ ነገሥቱ ታማኝ በተጨማሪም አማች ለሆኑት ለደጃዝማች ደስታ ዳምጠው (ኋላ ራስ) አስረከቧቸው።

አባ ጤና ኢያሱ በዚህ አኳኋን ከተያዙ በኋላ ፦

1ኛ/ ለዐሥራ አንድ ዓመታት በመልካም አያያዝ ወደኖሩበት ወደ ፍቼ እንደማይመለሱ፣

2ኛ/ ከተያዙበት ቦታ (ከጐጃም) ተነሥተው በአዲስ አበባ በኩል አድርገው በልዩ ባቡር ወደ ሐረር ጠቅላይ ግዛት እንደሚጓዙና ከዚያም በጋራ ሙለታ አውራጃ፣ አዲስ ወደሚዘጋጅላቸው የእስር ቤት መኖሪያቸው እንደሚሄዱ ተነገራቸው።

ልጅ ኢያሱ ይህንን ውሳኔ ሲሰሙ፣ ምን ያህል እንዳዘኑና ምን ያህል ተስፋ እንደቆረጡ፣ እጃቸውን ይዘው ለተቆራኟቸው የንጉሠ ነገሥቱ የብዙ ዘመን ታማኝ ለሆኑት ለደጃዝማች በዛብህ ስለሺ ገልጸውላቸዋል።

አባ ጤና ኢያሱ፣ ይህች ጉጃም ላይ የተያዙባት ሰኔ 4 ቀን 1924 ዓ.ም፣ ለሚቀጥሉት ሦስት ዓመታት የሚጠብቃቸው የእስር ቤት የጨለማና የስቃይ ሕይወት መጀመሪያ መሆኗን ያለ ጥርጥር ተገንዝበውታል። እንደዚሁም ለዐሥራ አንድ ዓመታት በራስ ካሣ ግቢ ውስጥ ተጠብቀው በኖሩበት ዘመን፣ ያንን የመሰለ የተመቸ መኖሪያ ቤታቸውንና ያንን የመሰለ እጅግ የተሟላ የወይዘሮ ጽጌ በሻህን መስተንግዶ ጥለው መውጣታቸው፣ በይበልጥ ጸጽቷቸዋል። ከዚህ ከፍቼ ከተማ ከነበራቸው መልካም ሕይወት ያፈናቀሏቸው ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖትም፣ ላይጠቅሟቸው ከፍተኛ ጉዳት ላይ እንደጣሏቸው በሚገባ ተረድተውታል። አክስታቸው ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱና የአያታቸው የምኒልክ ሚኒስትሮች፣ አልጋወራሽ ተፈሪንና አባ መቻል ሀብተጊዮርጊስን አሸንፈው፣ የሚታሰሩት በራስ ካሣ እጅ እንዲሆን ያስደረጉላቸው፣ ሥቃይና መከራ እንዳይደርስባቸው በማሰብ መሆኑን ያለጥርጥር አስታውሰውታል።

እንግዲህ ! ዛሬ ምን ይሻላቸዋል? እንደ ወላጅ እናት የሚራሩላቸው አክስታቸው ዘውዲቱ ምኒልክ፣ ከሁለት ዓመት በፊት ከዚህ ዓለም በሞት ተለይተዋል። በተጨማሪም፣ በእስራታቸው ዘመን ላይ ሰብዓዊ አመለካከትና በመጠኑም ቢሆን የለመዱት የተመቸ ሕይወት እንዳይጉድልባቸው ለማስደረግ፣ ተሰሚነት የነበራቸው የምኒልክ ታላላቅ ሰዎች ሁሉ አልቀዋል። በጉጃሜው መስፍን በራስ ኃይሉ ጥንስስ ሕዝብ አስነሥቶ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ለመጣልና የንጉሠ ነገሥትነቱን ዘውድ ለመጫን ያደረጉት ሙከራ ሲከሽፍ፣ ከእንግዲህ ወዲህ የአባ ጠቅል ተፈሪን እንጀት የሚያራራላቸው እንደማይሆን ያውቁታል። እንደዚሁም፣ በተፈሪ መኰንን ቦታ ራሳቸው ኢያሱ ቢሆኑ ኖሮ፣ ሥልጣናቸውን ለመቀማት በሚነሣባቸው ባለጋራ ላይ የሚወስዱት እርምጃ፣ በርኅራኄ የሚመሠረት እንደማይሆን ይገነዘቡታል። ስለዚህ፣ ኢያሱ አባ ጤና ያችን ከፍቼ ከተማ ከራስ ካሣ ግቢ አምልጠው የወጡባትን ቀን እየረገሙ፣ በሐረር ክፍለ ሀገር በጋራ ሙለታ አውራጃ የተዘጋጀላቸውን መራራ የእስር ቤት ጽዋ ከመቀበል በስተቀር ሌላ ዕድል አልነበራቸውም።

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ዘውድ አስነጥቁ እኔም የጉጃም ንጉሥ ለመባል እበቃለሁ በማለት፣ ልጅ ኢያሱን ከፍቼ እንዲያመልጡ ያስደረጓቸው ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት፣ ለፍርድ ሸንጐ ቀርበው የሞት ቅጣት ተበይኖባቸው ነበር። ነገር ግን ንጉሠ ነገሥቱ ለጉጃሙ መስፍን ፍርዱን ለውጠው ሀብታቸውን መንግሥት እንዲወርስና በአንድ በተለየ ሥፍራ በግዞት እንዲኖሩ በማድረግ ሲያሻሽሉላቸው፣ የምኒልክ የልጅ ልጅ በሆኑት በኢያሱ ላይ የወሰኑባቸው የጋራ ሙለታ እስር ቤት ብርቱ ቅጣት ነው፣ የሚል ወቀሳ መነዛቱ አልቀረም ነበር። ይሁን እንጂ፣ ይህን ውሳኔ ለማሻሻል የሚሞክር አማላጅ ባለመኖሩ፣ ልጅ ኢያሱ ከተያዙበት ከሰኔ 1924 ዓ.ም ጀምሮ፣ ሕይወታቸው አለፈ ተብሉ ኃዘኑ በይፋ እስከተገለጸበት እስከ ህዳር 11 ቀን 1928 ዓ.ም ድረስ፣ ለሦስት ዓመት ከአራት ወር ብዙ ስቃይና መከራ መቀበላቸውን መካድ አይቻልም። በፍቼ ከተማ በራስ ካሣ ቤት በእስር ተጠብቀው በኖሩበት ዘመን፣ የማረፊያ ቤታቸውና አኗኗራቸው እንዴት እንደነበረ የሚነግረን ስናገኝ፣ የጋራ ሙለታ የስቃይ ሕይወታቸውን በትክክል የሚተርክልን በማጣታችን

እጅግ እናዝናለን። እስከ ዛሬ የምንሰማው ሁሉ ከዓይን ምስክር የተገኘ ሳይሆን፤ በአፈ ታሪክ ላይ የተመሠረተ ስለሆነ፤ ለእኛ ለታሪክ ተመራማሪዎች የትኛውን ተቀብለን የትኛውን እንደምንጥል ለመወሰን ቀላል አልሆነልንም።

## የአሟሟታቸው ሁኔታ

በጋራ ሙለታ ለሦስት ዓመታት የተሰቃዩት እስረኛ የሞቱት፤ በቆየ ሕመም ወይም እንደልብ ድካም በመሳሰለው በድንገተኛ አደጋ ሳይሆን፤ ተገድለው ነው ብሎ ብዙ ሰው ያምናል። ስለ አሟሟታቸው በያለበት በሰፊው የተወራው ዓይነቱ ብዙ ቢሆንም፣ ወደ እውነቱ ሊቃረቡ ይችላሉ ተብለው የሚገመቱት ዜናዎች፣ በሁለት የሚከፈሉ ናቸው።

ይኸውም፤ አንዱ ወገን በመርዝ የተለወሰ ምግብ እንዲበሉ በማድረግ ነው ሲል፣ ሌላው ደግሞ በጭለማ አነጣጣሪ ተኳሽ ተመድቦ በጥይት ተገድለዋል የሚል ነው። ያም ሆነ ይህ፤ ልዩነቱ የአገዳደሉ ዓይነት ነው እንጂ የሁለቱም ወገኖች ዕምነት የሚመረኮዘው፤ ንጉሠ ነገሥቱ ኢትዮጵያን ለመውረር ከመጣው ከፋሽስት ጦር ጋር ለመዋጋት ወደ ማይጨው ዘመቻ ከመሄዳቸው ከሰባት ቀን በፊት፣ ልጅ ኢያሱ እንዲሞቱ ዝግጅት ተደርጐ መገደላቸውን ነው።

አንዳንድ ሰዎች በተፈሪ መኰንን ላይ የሚገልጹት ቅሬታ፤ ልጅ ኢያሱ በሚያዝያ 1913 ዓ.ም ከተያዙ በኋላ፤ ዐሥራ አራት ዓመት ሙሉ በእስር ቤት አቆይቶ ከመግደል፤ ገና እንደተያዙ ወዲያውኑ ለፍርድ አቅርበው ለምን የሞት ቅጣት አላስፈጸሙባቸውም ? የሚል ነው። በዚህ ሐሳብ ላይ አስተያየት ከመስጠት በፊት፣ የታሪኩን ሂደት ጥቂት ወደ ኋላ መለስ ብሎ ማተኮርና ማመዛዘን የሚያስፈልግ ይሆናል።

ልጅ ኢያሱ ከሥልጣን ከወረዱበት ከመስከረም 1909 ዓ.ም ጀምሮ እጅን አልሰጥም ብለው፤ ከአራት ዓመታት በላይ በየጫካውና በየበረሀው ሲዋጉ ከኖሩ በኋላ፤ በትግራይ ከተሸሸጉበት ገዳም ምንም ዓይነት አደጋ ሳይደርስባቸው በሕይወት መያዛቸው፤ እክስታቸውን ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱን እጅግ አድርጐ ሲያስደስት፤ ለአልጋወራሽ ተፈሪ ሰላም የሚሰጥ ሆኖ እንዳልተገመተ በግልጽ የሚታይ ነበር። ምክንያቱም፤ ልጅ ኢያሱ ተይዘው ቢታሰሩም፤ በሕይወት እስካሉ ድረስ፤ በስማቸው በመጠቀም የተፈሪ መኰንን ተቀዋሚዎች አንዳንድ የዓመፅ ሙከራ ለማድረግ ስለሚያስችላቸው ነው። ለዚህም፤ ከደረሱት ከብዙዎች ሙከራዎች መካከል እጅግ ጕልቶ የሚታየውና እንደምሳሌ ሆኖ የሚቀርበው፤ አንደኛው፤ የንጉሥ ሣህለሥላሴ የልጅ ልጅ የሆኑት ወይዘሮ ፀሐይወርቅ ዳርጌ፣ አልጋወራሽ ተፈሪን ለማስገደልና ልጅ ኢያሱን ከእስር ቤት አስወጥቶ ለማንገሥ በመስከረም 1918 ዓ.ም ያቀዱት ሐሳብ ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ ይህ በግንቦት 1924 ዓ.ም ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት የጠነሰሱት ሴራ ነው። ሌሎችም ዝርዝራቸው ባይገለጽም ይህን የመሳሰሉት ሴራዎች ተሞክረው ነበር።

እንግዲህ ! የልጅ ኢያሱ ተይዞ በእስር ቤት መኖር፤ ለወደፊቱ ንጉሠ ነገሥት ለአልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን ሰላም የሚሰጥ እንዳልነበረ በግልጽ የሚታይ ነው። ነገር ግን ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱና ዋና

ዋናዎቹ የምኒልክ ሰዎች በሕይወት እስካሉ ድረስ ፤ ተፈሪ መኰንን ኢያሱን ለፍርድ አቅርበው የሞት በቃ ለማስፈረድና ፍርዱንም ለማስፈጸም አይችሉም ነበር። የምኒልክ መኳንንት፤ ምንም እንኳ ኢያሱ ሚካኤል አያታቸው የጣሉባቸውን አደራ ባለመጠበቅ ባሳዩት ድርጊት ከመሪነት ሥልጣን መወገዳቸውን ሁሉም ያመኑበት ቢሆንም፤ የአባ ዳኘውን ልጅ በፍርድ ሸንጐ ላይ ቆሞ የሚፋረድ ማነው ? ለሚለው ጥያቄ እኔ ነኝ ብሎ የሚቀርብ ደፋር አልነበረም። ይህ ሁሉ ቀርቶ፤ ኢያሱ በሰላም ከተያዙ በኋላ የሚታሰሩት፤ በሐረር በራስ መኰንን ታማኝ አሽከሮች እጅ እንዲሆን፤ አልጋወራሽ የነበራቸውን ፍላጐት እንኳን መፈጸም አልቻሉም። ንግሥቲቱና የምኒልክ ሰዎች የአልጋወራሹን ሐሳብ ተቃውመው በራስ ካሣ እጅ ተይዘው እንዲቆዩ ያደረጉበት ዋናው ምክንያት፤ እስረኛው መከራና ስቃይ እንዳይደርስባቸው በማሰብ ስለሆነ፤ ለልጅ ኢያሱ ትልቅ ዕድል ሆኖ ነበር።

ምን ይሆናል ? ..... ኢያሱ አባ ጤና በተለይ ሩኅሩኅ በሆኑት በአክስታቸው ብርታት ይህንን ያገኙትን የተመቸ ማረፊያ፤ እስከ መጨረሻው ሕይወታቸው ሳይጠቀሙበት ቀሩ። ለዐሥራ አንድ ዓመታት በመልካም ሁኔታ ከኖሩበት ከዚህ ከራስ ካሣ ግቢ አምልጠው ከጐጃሙ መስፍን ሴራ ውስጥ መግባታቸው፤ የመጨረሻውን የእስር ቤት ሕይወታቸውን እጅግ የጠበቀና የስቃይ ዓለም እንዲሆን አደረገባቸው።

ሌላው ደግሞ የልጅ ኢያሱን ዕድሜ ያሳጠረው፤ የፋሽስት ጣልያን ኢትዮጵያን ለመውረር እየገሰገሰ መምጣቱ ነው። በዚያን ጊዜ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ዘውዳዊ መንግሥታቸውን ለመቀማት በሚገባ ተዘጋጅቶ የመጣባቸውን ጠላት፤ አሸንፈው ወደመጣበት ለመመለስ የሚያስችል ኃይል እንደሌላቸውና አገሪቱም በፋሽስት እንደምትያዝ ደህና አድርገው ያውቁ ነበር። ሆኖም፤ እስከሚቻላቸው ለመዋጋት በህዳር 18 ቀን ራሳቸው ጦር ይዘው ወደ ማይጨው ለመዝመት ሲወስኑ፤ ያለ ጥርጥር ልጅ ኢያሱን ለሙሶሊኒ የፖለቲካ መጠቀሚያ ትተው መሄድ አልፈለጉም። በዚህ ሁኔታ ህዳር 11 ቀን 1928 ዓ.ም ከንጋቱ 12 ሰዓት ላይ የልጅ ኢያሱ ድንገተኛ ሞት መርዶ ተነገረ ተብሎ በቤተመንግሥቱ ያ ሁሉ የሐዘን ቴያትር የተደረገው፤ እንዲሁ ለይምሰል ነው እንጂ፤ ሕይወታቸው ያለፈው በሕመም ነው ብሎ የተቀበለ ወገን አልነበረም። ከዚህ በቀር ደግሞ መሞታቸው አሳዛኝ ነው ተብሎ በንጉሠ ነገሥቱ ግቢ ውስጥ የሐዘንተኛ መቀበያ ወንበሮች ሲደረደሩ፤ በሌላ በኩል ደግሞ አስከሬናቸው ለተወላጆቻቸው ተሰጥቶ በሥርዓት እንዳይቀበሩ መከልከሉ፤ የሰውየው አሟሟት በሕመም አለመሆኑን ያመለክታል። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ስለ አሟሟታቸው ዝርዝሩን ታሪክ ለማቅረብ የተመኘው ሁሉ ባይሳካለትም፤ ኢያሱ አባ ጤና ከዚህ ዓለም የተለዩት በሕመም ወይም በድንገተኛ አደጋ ሳይሆን በፖለቲካ ውሳኔ መሆኑን ያምንበታል።

**መረጃ፤** ልጅ ኢያሱ በሰላሌ አውራጃ በፍቼ ከተማ ተይዘው በጥበቃ በኖሩበት ዘመን፤ ሕይወታቸው እንዴት እንደነበረና በመጨረሻም ለማምለጥ የቻሉት በምን ዝግጅት እንደሆነ ለደራሲው ያስረዱት፤ የልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ የልጅ ልጅ የሆኑት ክቡር ደጃዝማች ብርሃነመስቀል ደስታ ናቸው። ደጃዝማች ብርሃነመስቀል፤ በቀ.ኃ.ሥ ዘመነ መንግሥት ብዙ ጊዜ በጠቅላይ ግዛት እንደራሴነት ካገለገሉ በኋላ በመጨረሻ የሕግ መወሰኛ ምክር ቤት አባል ነበሩ።

# ምዕራፍ ፫

## የንጉሡ ነገሥቱ ዘመቻ

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከአንድ ወር በፊት ወደ ሰሜን ግንባር የሚዘምተውን የኢትዮጵያን ጦር ሲያሰናብቱ፤ « ... በሰላሙ ጊዜ የሚገዛችሁ ንጉሠ ነገሥት፤ በጦርነቱም ሰዓት ከመካከላችሁ ሆኖ ደሙን ለማፍሰስ ቆርጧል ... » ሲሉ በተናገሩት መሠረት፤ እንደ ኢት.አቆ ኅዳር 18 ቀን 1928 ዓ.ም (27/11/35) ከአዲስ አበባ ተነሥተው ወደ ሰሜን ግንባር የሚያደርጉትን ጉዞ ጀመሩ። ንጉሠ ነገሥቱ መናገሻ ከተማቸውን ለቅቀው ሲወጡ፤ ተመልሰው ለመምጣታቸው ምንም ዓይነት ዋስትና ስላልነበራቸው፤ በኢትዮጵያ ባህልና ወግ መሠረት አስፈላጊውን ኑዛዜ ማድረጋቸው ታውቆ ነበር። ይሁን እንጂ፤ የኑዛዜው ቃል እስከዛሬ ድረስ ሳይገለጽ ቢቀርም፤ ጉዳዩን እናውቀው ነበር ከሚሉት ሰዎች ዘንድ እንደተገኘው፤ « ... ንጉሠ ነገሥቱ በጦሩ ሜዳ ላይ ሲዋጉ ሕይወታቸው ሲያልፍና፤ ጠላት በድል አድራጊነት ወደ አዲስ አበባ ሲገሰግስ፤

1ኛ/ ቤተሰቦቻቸው እቴጌ መነንና ልጆቻቸው፤ እንደዚሁም ተወላጆች የሆኑት ንጉሣዊ ቤተሰቦች (በጠቅላላው ቁጥራቸው ከሐያ የማይበልጡ) እንግሊዝ ለጋሲዮን ገብተው ስደተኝነት እንዲጠይቁና ከዚያም ወደ ኢየሩሳሌም እንዲሄዱ፤

2ኛ/ ከሞት የተረፉት የታወቁት የጦር አለቆች፤ በአንድ ለጠላት ምቹ ባልሆነ አውራጃ ተሰብስበው ከመካከላቸው በዕድሜና በአገልግሎት፤ በሕዝብም ዘንድ ታዋቂ የሆነውን አንዱን መርጠው የሟቹ ንጉሠ ነገሥት እንደራሴ አድርገው እንዲሾሙና፤ ኢትዮጵያ አልሞተችም በማለት ድምፃቸውን ለዓለም መንግሥታት እያሰሙ ትግላቸውን እንዲቀጥሉ፤

3ኛ/ የጠላትን ገዥነት አንቀበልም ብለው መሥዋዕትነትን በመቀበል በየጫካው እየገቡ ለነፃነት የሚዋጉትን አርበኞች፤ ሕዝቡን እያስተባበሩ መሣሪያና ስንቅ እንዲያቀብሏቸው እንዲያደርጉ፤ አደራ የሚል ነው።

የዚህ ኑዛዜ ቃል አንዱ ግልባጭ የተሰጠው ለእጨጌ ገብረጊዮርጊስ (ኋላ አቡነ ባስልዮስ ፓትርያርክ ዘ-ኢትዮጵያ) ሲሆን፤ ከጦርነቱ ፍጻሜ በኋላ ሐሳቡ በተግባር እንደማይውል ቢታወቅም፤ ሰነድነቱ ለታሪክ ይጠቅማል ተብሎ እንዲቀመጥ አልተደረገም ይባላል።

በመግቢያው ላይ እንደተጠቀሰው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በኢት አቆ/ ኅዳር 18 ቀን 1928 ዓ.ም ከአዲስ አበባ ተነሥተው ከሁለት ቀናት በኋላ ወሎ ዋና ከተማ ደሴ ሲደርሱ፤ ለማረፊያ ተዘጋጅቶ የጠበቃቸው የጣልያን ቆንስል መኖሪያ ቤት የነበረው ነው። የሙሶሊኒ ጣልያን ኢትዮጵያን ለመያዝ ዝግጅት የጀመረው

ካለፉት ሦስት ዓመታት ጀምሮ ስለሆነ፣ የኢትዮጵያን መንግሥት ወዳጅነትን ለማስፋፋት ይጠቅማል ብሎ በማታለል በኢትዮጵያ ዋና ዋና ከተሞች በተለይም፣ በጐንደርና በትግራይ፣ በጐጃምና በወሎ፣ ሰፋፊ የቆንስላ ቢሮዎች ከፍቶ የፕሮፓጋንዳና የስለላ ተግባሮች የሚያከናውኑ ፋሽስቶችን አስፍሮባቸው ነበር። በጥቅምት ወር መጀመሪያ ላይ የሙሶሊኒ ጦር ኢትዮጵያን መውረር እንደጀመረ፣ እነዚህ ቆንስሎች ሰነዶቻቸውን ብቻ በመያዝ በየቤታቸው ያሏቸውን የቢሮና የመኖሪያ ዕቃዎች ሁሉ በቅርቡ ተመልሰው እንደሚያገኙት እርግጠኛ በመሆን፣ ለጊዜው ትተውት ወደ አገራቸው ተመልሰው ነበር። በደሴ ከተማ ላይ የሚገኘው የጣልያን ቆንስል መኖሪያ ቤት፣ ከቀድሞው ከንጉሥ ሚካኤል ግቢ የተሻለ ሆኖ በመገኘቱ፣ ከእንግዲህ ወዲህ ጣልያን ተመልሶ አይመጣም በሚል ዕምነት፣ ከኅዳር 20 ቀን 1928 ዓ.ም ጀምሮ **መርሖ - ቤተመንግሥት** ተብሎ ተሠይሞ፣ የንጉሠ ነገሥቱ ማረፊያ ሆነ። በግዕዙ "**መርሆ** " ማለት መምሪያ ስለሆነ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በሰሜንና በደቡብ በኩል የመጣውን የፋሽስት ጦር እንዲከላከሉ በየግንባሩ ለመደቧቸው የጦር አለቆች ሁሉ መምሪያ የሚሰጡት ከዚህ በደሴ ከተማ አዲስ ከተቋቋመው ከ "**መርሆ ቤተመንግሥት**" ነበር።

ደሴ ከተማ ከደረሱበት እንደ ኢት.አቆ ከኅዳር 20 ቀን እስከ የካቲት 13 ቀን 1928 ዓ.ም ድረስ፣ በመርሆ ቤተመንግሥት በቆዩባቸው በሰማኒያዎቹ ቀናቶች ውስጥ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በራዲዮ መገናኛዎች በመጠቀም፣

1ኛ/ በየግንባሩ የተሰለፉት የጦር አዝማቾች፣ ከጠላት ጋር በየዕለቱ ስለሚያደርጉት ጦርነት የሚልኩላቸውን ሪፖርት እየተቀበሉ አስፈላጊውን መምሪያ መስጠት፣

2ኛ/ አዲስ አበባ ካሉት ሚኒስትሮቻቸው፣ በተለይም ስለ ሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትራቸው ከብላቴን ጌታ ኅሩይ ጋር መመካከር፣ ቀጥሎም ለሕዝብ ስለሚገለጹት የጦርነት ዜናዎች እንደማስታወቂያ ሚኒስትር አድርገው ከመደቧቸው ከአቶ መኰንን ሀብተወልድና የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ፀጥታ ኃላፊ ከሆኑት ከብላታ ታከለ ወልደሐዋርያት ጋር፣ ቢያንስ በቀን ሁለት ጊዜ በራዲዮ መገናኛ ትዕዛዝ መስጠት፣ የንጉሠ ነገሥቱ የዕለት ተግባሮች ነበሩ።

ንጉሠ ነገሥቱ ለጦርነቱ አካሄድና ለመንግሥታቸውም አስተዳደር ዋና መምሪያቸውን ደሴ ላይ ማድረጋቸው ከታወቀ በኋላ፣ ጠላት በየጊዜው ያጠቃ የነበረው በአውሮፕላን ቦንብ በመጣል እንጂ፣ የምድር ጦሩን እያጓዘ ትግራይን አልፎ ወደ ወሎ ለመቅረብ አልጀመረም። ስለዚህም በደሴ ከተማ ዙሪያ በሚገኙት ተራራዎች ላይ የጠላትን የጦር አውሮፕላኖች ለመምታት ኦርሊኮን የተባሉት አራት መሣሪያዎች ተጠምደው እንዲጠባበቁ ስለተደረገ፣ ከእነዚህ ተራራዎች አንዱ " **ሳላይሽ** " የተባለው ቦታ ንጉሠ ነገሥቱ እንደ አንድ ወታደር ቆመው የሚታኰሱበት እንዲሆን ተዘጋጅቶ ነበር። በዚህም መሠረት፣ እንደ ኢት አቆ/ ከኅዳር 29 ቀን 1928 ዓ.ም ጀምሮ ደሴን ለቅቀው ወደ ማይጨው ዘመቻ እስከሔዱበት እስከ የካቲት ወር አጋማሽ ድረስ፣ ቢያንስ በቀን አንድ ጊዜ ሳላይሽ



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጦር ሲያስናብቱ

ተራራ ላይ እየወጡ፣ በፋሽስት የጦር አውሮፕላኖች ላይ ራሳቸው ሲተኩሱ ይውሉ እንደነበረ፣ በዚያን ጊዜ ከጃንሆይ ተከታዮች አንዱ የሆኑት የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ (ኋላ ም/ጸሐፊ ትዕዛዝ) በታሪክ ማስታወሻቸው ላይ በዝርዝር ገልጸውታል:: *

ንጉሠ ነገሥቱ መናገሻ ከተማቸውን አዲስ አበባን ለቅቀው የጦርነቱን መምሪያና የአገሩን አስተዳደር ደሴ ከተማ ላይ ሲያቋቁሙ፣ አስከትለዋቸው የመጡት ታላላቅ ሰዎች፡-

1. ፊታውራሪ ብሩ ወልደገብርኤል የቀድሞ የጦር ሚኒስትር (ኋላ ራስ)

2. ደጃዝማች ኃይለሥላሴ አባይነህ፣ የቅምብቢትና የትቤ አውራጃ ገዥ፣ (የጃንሆይ ልዩ ባለሟል የራስ እምሩ አባት)

3. ደጃዝማች ወልደአማኑኤል ሐዋስ፣ የቀድሞ የክብር ዘበኞች አለቃ፣

4. ደጃዝማች ወንድራድ ድፋባቸው፣ የመርሐ ቤቴ ገዥ

5. ደጃዝማች አደፍርሰው ይናዱ፣ የግቢ ዘበኞች አዛዥ (ኋላ ራስ)

6. ቀኛዝማች ተክለማርቆስ ወልደገብርኤል፣ የፖስታ ሚኒስትር ነበሩ::

ከእነዚህ ታላላቅ ሰዎች መካከል ምንም እንኳ አንዳንዶቹ ከዚህ ቀደም በጦር ሜዳ የዋሉና የአዝማችነት ልምድ ያላቸው ቢሆኑም፣ የማይጨው ጦርነት እስከተጀመረ ድረስ ደሴ ላይ በቆዩበት ጊዜ ውስጥ ዋናው ተግባራቸው ንጉሠ ነገሥቱን በምክር ከመርዳት በስተቀር ወደየግንባሩ ሔደው በጦርነቱ ላይ ተካፋይ እንዲሆኑ አልተደረገም::

* ገብረወልድ እንግዳወርቅ የማይጨው ዘመቻና የጉዞው ታሪክ (1947 ዓ.ም)

# ምዕራፍ ፱

## የላቫልና ሖር ፤ የእርቅ ፕላን*

ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ በደሴ ከተማ ባቋቋሙት የጦር መምሪያ ቢሮአቸው ላይ እንዳሉ፤ እንደ ኢት አቆ/ ታህሣሥ 6 ቀን 1928 ዓ.ም (16/12/35) የፈረንሣይ ጠቅላይና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ፒየር ላቫልና የታላቋ ብሪታንያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሚስተር ሳሙኤል ሖር፤ በጦርነት ውስጥ የሚገኙትን የኢትዮጵያንና የጣልያንን መንግሥታት ለማስታረቅ አጥንተው ያቀረቡት የዕርቅ ፕላን ደረሳቸው። የእነዚህ ሰዎች ሐሳብ ባጭሩ በሁለት መልክ የተዘጋጀ ነበር። ይኸውም፡-

የመጀመሪያው፤ ከኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ በሰሜን በኩል ከአክሱም በስተቀር ሌሎቹን የትግራይን አውራጃዎችና በደቡብ በኩል ደግሞ ኦጋዴንን በሙሉ ለሙሶሊኒ ጣልያን እንዲሰጥ የሚያደርግ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ፤ በሌሎቹ በደቡብ አውራጃዎች በተለይም በከፋ፣ በሲዳሞና በባሌ በኩል የሙሶሊኒ መንግሥት በሙሉ ሥልጣን የኤኮኖሚ ልማት ለማካሄድ እንዲያስችለው የሚጠይቅ ነው። ይህ ሁሉ ከተደረገ በኋላ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ዛሬ በአለንበት በሐያ አንደኛው ክፍለ ዘመን የአማራ ክልል የተባሉትን አውራጃዎች፤ ሸዋንና ጐጃምን፤ ጐንደርንና ወሎን፤ ከትግራይም በኩል የኢትዮጵያ ታሪክ መሠረት የሆነውን አክሱምን ብቻ ይዞ፤ ሌሎቹን በሙሉ በግዛትም መልክ ሆነ በኤኮኖሚ ልማት አስተዳደር፤ ለሙሶሊኒ መንግሥት ካስረከበ በኋላ፤ በፋሽስት መንግሥት መልካም ፈቃድ በአሰብ በኩል የባሕር በር መተላለፊያ ተለክቶ እንዲሰጠው ይደረጋል የሚል ነው።

ከሁሉም ይበልጥ እጅግ የሚያስገርመው፤ ይህን የኢትዮጵያን መብት የሚገፍ ፕላን ሲያቀርቡለት፤ ዲክታተሩ ለመቀበል አለመፈለጉ ነው። ሊግ ኦፍ ኔሽን የወሰነበት የኤኮኖሚ ዕገዳ የነዳጅ ዘይትን የሚጨምር ቢሆን ኖሮ፤ ሙሶሊኒ ከኢትዮጵያ ጋር የዕርቅ ንግግር ለመክፈት አዘንብሎ እንደነበረ ይታወሳል። ነገር ግን ወዲያውኑ፤ አንደኛ/ የጃፓንና የአሜሪካ መንግሥታት የነዳጅ ዘይት እንደሚሸጡለት ስላስታወቁት፤ ሁለተኛ/ ሊግ ኦፍ ኔሽንም በሚደረጉት የኤኮኖሚ ዕገዳዎች ዝርዝር ውስጥ የነዳጅ ዘይትን ጉዳይ ሳይጨምረው በመቅረቱ፤ ዲክታተሩ ሥጋቱ ስለተወገደለት በኢትዮጵያ ላይ የጀመረውን ጦርነት ለመቀጠል የልብ ልብ ተሰማው። ከዚህ በላይ ደግሞ በጦርነቱ አካሄድ አንዳንድ ድል በማግኘት አድዋንና ዋና ዋናዎቹን የትግራይን አውራጃዎች ከያዘ በኋላ፤ የፈረንሣይና የታላቋ ብሪታንያ መንግሥታት ያቀረቡለትን የዕርቅ ሐሳብ ለመቀበል ፈቃደኛ አልሆነም።

እንደ እውነቱ ከሆነ፤ የፈረንሣይና የታላቋ ብሪታንያ መንግሥታት የሊግ ኦፍ ኔሽንን መሠረታዊ ዓላማ ተመርኩዘው የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር ከልብ

---

* PLAN LAVAL-HOOR Societé des Nations C.482 M.258. 1935

የሚፈልጉ ቢሆኑ ኖሮ፣ የሙሶሊኒን የግፍ ሥራ ለማቆም፣ ሁለት ዓይነት እርምጃዎች ብቻ ቢወሰዱበት በቂ መሆን ይችል ነበር። ይኸውም፡-

1. የፋሽስት መንግሥት ኢትዮጵያን በጦር ለመውጋት ከመጠን በላይ የሆኑ ወታደሮችና መሣሪያዎች በመርከብ ጭኖ ሲያጓጉዝ፣ ሁለቱም መንግሥታት ባለሙሉ ሥልጣን በሆኑበት በስዊዝ ካናል ላይ ማለፍ አትችልም ብለው ቢያግዱት፣

2. በሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ላይ በተወሰነው መሠረት ከሚደረጉት የኤኮኖሚ እገዳዎች መካከል፣ ዋና ጉዳይ የሆነው የነዳጅ ዘይት ተጨምሮ ቢሆን ኖሮ፣

የሙሶሊኒ መንግሥት የጀመረውን ጦርነት አቁሞ ለሰላም ንግግር ከመዘጋጀት በስተቀር ሌላ ምርጫ አይኖረውም ነበር። አሁን ግን ዲክታተሩ እነዚህ ሁለት የሚሠጋባቸው ዋና ዋና ችግሮች እንደማይደርሱበት እርግጠኛ ከሆነ በኋላ፣ ጦርነቱን በመቀጠል ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ከማድረግ በስተቀር የላቫልንና የሖርን የዕርቅ ፕላን ለመቀበል ፈቃደኛ አለመሆኑ የሚያስደንቅ አይደለም። ለነገሩ፣ ዲክታተሩ በዚህ በቀረበለት የዕርቅ ሐሳብ ጥቅሙ ምን ያህል መሆኑን ተረድቶ እስማማለሁ ቢል እንኳን፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጨርሶ እንደማይቀበሉት የታወቀ ነበር። በመሠረቱ አፄ ቴዎድሮስ፣ አፄ ዮሐንስና አፄ ምኒልክ፣ መሥዋዕትነትን እየተቀበሉ ታግለው ያቆዩትን የኢትዮጵያን የግዛት አንድነትና ነፃነት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እየቆራረሱ ለጣልያን ኮሎኒያሊስት ለመስጠት ይስማማሉ ብሎ መጠበቅ አይቻልም።

እ.ኤ.አ ታህሣሥ 16 ቀን 1935 ዓ.ም በሊግ ኦፍ ኔሽን ጽሕፈት ቤት በኩል ለንጉሠ ነገሥቱ በቴሌግራም የተላለፈው የላቫልና የሖር የዕርቅ ፕላን በደሴ መርሖ ቤተመንግሥት እንደ ደረሳቸው፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩን ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደ ሥላሴንና ሌሎቹንም ዋና ዋና አማካሪዎቻቸውን ይዘው ከመረመሩ በኋላ የሰጡት መልስ፣ የፕላኑ ባለቤቶች የሆኑትን ፈረንሣይንና እንግሊዝን የሚነቅፍ ብቻ ሳይሆን፣ የመንግሥታት ማህበርም አሠራር ከዓላማው ውጭ መሆኑን ደህና አድርጎ የሚያስገነዝብ ነበር።

« ... **አንድ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነ መንግሥት፣ በጦርነት ነፃነቱን ለመግፈፍ በግፍ ከተነሣበት አገር ጋር እንዲታረቅና ሰላም እንዲመሠረት፣ ተጠቂው አገር ለአጥቂው ካሣ እንዲሆን ከግዛቱ ቆርሶ መሬቱን እንዲሰጥ ሐሳብ የሚያቀርብ አስታራቂ ዳኛ ከዚህ ቀደም ታይቶ የማይታወቅ ስለሆነ፣ ተቀባይነት የለውም። እንደዚሁም፣ በአባል አገሮች መካከል ኃይለኛው ደካማውን እንዳያጠቃ፣ የሁሉንም ነፃነትና መብት በእኩል ደረጃ እንዲያስከብር ኃላፊነት የተቀበለው የመንግሥታት ማህበር፣ አንድ በግፍ የተጠቃ አገር ከግዛቱ አብዛኛውን መሬት ቆርሶ ለአጥቂው ኮሎኒያሊስት ቢሰጥ፣ ሰላም ሊገኝ ይችላል ብሎ ሐሳብ ለማቅረብም ሆነ ለመጠየቅ ተግባሩ አይደለም። ስለዚህም፣ ኢትዮጵያ በፈረንሣይና በታላቋ ብሪታንያ ጠቅላይና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮች ተጠንቶ በሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት በኩል የቀረበላትን የዕርቅ ፕላን ፍጹም የማትቀበለው መሆኗን ታስታውቃለች። ይህም ሲሆን፣ የመንግሥታት ማህበር የአባል አገሮችን ነፃነትና መብት ለመጠበቅ ያለበትን ኃላፊነት አክብሮ ትክክለኛውን ፍርድ እንደማይነፍጋት**

ተጠቂዋ ኢትዮጵያ እስካሁን ተስፋዋን ያልቆረጠች መሆኗ እንዲታወቅላት ትጠይቃለች ... »

ይህ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተሰጠው መልስ፤ ዤኔቭ ከመንግሥታት ማህበር ጽሕፈት ቤት ሲደርስ፤ የሙሶሊኒ ወዳጆች እነ የሴፍ አቬኖል እጅግ ተገረሙ። ንጉሥ ተፈሪ የአማራ ተወላጅ በመሆናቸው፤ በኢትዮጵያ ውስጥ ላሉት የአማራ አውራጃዎች በሙሉ የንጉሠ ነገሥት ሥልጣናቸው ታውቆላቸው በምቾት እንዲኖሩ የታሰበላቸውን አልቀበልም ይላሉ ብለው አልጠበቁም። የእነ አቬኖል አስተያየት፤ የላቫልንና የሖርን ፕላን ምንም እንኳ ሙሶሊኒ ላለመቀበል በቅድሚያ ቢያንገራግርም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እስማማለሁ ቢሉ ኖሮ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት አባላት እንደምንም ብለው ሙሶሊኒን ማሸነፍ ይችሉ ነበር የሚል ነው።

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የሰጡት መልስ ዤኔቭ ላይ በይፋ እንደታወቀ፤ በተለይ በእንግሊዝ አገር ሕዝቡና በፓርላማው ያሉት የሊበር የፖለቲካ ፓርቲ አባሎች፤ በኮንሴርቫተሩ በስታንሌይ ባልድዊን (Stanley Baldwin) መንግሥት ላይ ከፍ ያለ ተቃውሞአቸውን ገለጹ። ይህም ተቃውሞ በግፍ ተነሥቶ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ጦርነት የከፈተውን ፋሽስት ለመጥቀም ሲባል፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ከፈረንሣይ ጋር ተባብሮ ያዘጋጀው የዕርቅ ፕላን የሚያሳዝን ብቻ ሳይሆን የሚያሳፍርም ነው በማለት፤ የኮንሰርቫተሩን መንግሥት ለመጣል የሚያመራ ሆነ። በዚህ ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ስታንሌይ ባልድዊን ውስጥ ውስጡን ስሕተቱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ እንደሆነ በማስመሰል፤ ላይ ላዩን ደግሞ ጥፋቱ የራሱም ጭምር መሆኑን በማሰማት፤ ሳሙኤል ሖር ሥልጣኑን እንዲለቅ አስደርጐ የኮንሴርቫቲቩን መንግሥት ከመፍረስ አዳነው። ወዲያውም፤ በዚህ በኢትዮጵያ ጉዳይ የምትከተለው ፖሊሲ ትክክል አይደለም ብለው የተነሡበትን በተለይም የኮንሴርቫቲቭ ፓርቲ አባሎችን ዝም ለማሰኘት፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ላይ የፋሽስትን መንግሥት ሳያመነታ ይቃወም የነበረውንና በተቻለውም በኢትዮጵያ ላይ የሚፈጸመውን ግፍ ለመከላከል ሲጥር የታየውን አንቶኒ ኢደንን፤ በሳሙኤል ሖር ቦታ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አደረገው። የላቫልና የሖር ፕላን፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ለመታየት በቀረበ ጊዜ፤ አንቶኒ ኤደን የመቃወም ድምፅ በማሰማቱ፤ በኮንሴርቫቲቮቹ ብቻ ሳይሆን በሊበሮቹም ዘንድ መልካም አስተያየት ተሰጥቶት ነበር።

እንግዲህ ! በዚህ በኢትዮጵያና በጣልያን ዕርቅ ጉዳይ ሎንደን ላይ የተለኮሰው የፖለቲካ እሳት፤ ሎንዶን ላይ ከስሞ አልቀረም። ወደ ፓሪስ ተሻግሮ፤ በፒየር ላቫል መንግሥት ላይ ከሎንዶን የበለጠ ከፍ ያለ ጣጣ አስከትሏል። በፈረንሣይ ፓርላማ ያሉት የራዲካልና የሶሲያሊስት ፓርቲ አባሎች፤ የኢትዮጵያ ደጋፊዎች በሆኑት በእነ ኤድዋርድ ሔሪዮ (Edouard Heriot) መሪነት፤ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ከፋሽስቱ መሪ ጋር የዘረጋውን ወዳጅነት አጠንክረው በመቃወም ባደረጉት ትግል፤ የሳሙኤል ሖር ሽረት ከተከናወነ ከአምስት ሳምንታት በኋላ፤ ፒየር ላቫልንም ከሥልጣን አወረዱት።

የሙሶሊኒ ዋና ደጋፊ የሆነው የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፤ ከሥልጣን መውረዱን እንደተረዳ፤ ለወዳጁ ለዱቼ በላከው የኑዛዜ ደብዳቤ ላይ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ ጉዳይ የፋሽስቱን መንግሥት ለመርዳት፤ በልዩ ልዩ ጊዜያቶች ያደረጋቸውን ጥረቶች ዘርዝሮ ለማስረዳት

ሞክሯል። ፒየር ላቫል ለቤኒቶ ሙሶሊኒ በላከው ምሥጢራዊ ደብዳቤ የገለጻቸው ዋና ዋና አስተያየቶች፣ መንፈሳቸውና አቀራረባቸው እንደሚከተሉት ነበሩ።*

## 1ኛ. እ.ኤ.አ ነሐሴ 16 ቀን 1935 ዓ.ም፤

የታላቋ ብሪታንያ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ሚኒስትር የሆነውን አንቶኒ ኤደንን እንደምንም አግባብቼ ፓሪስ ላይ ተሰብስበን በሰፊው ካጠናን በኋላ፤

ሀ/ ከኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ለኤኮኖሚ ልማት ምቹዎች ናቸው የሚባሉት እንደ ኦጋዴንና ከፋ የመሳሰሉት አውራጃዎች፤ በንጉሡ በጐ ፈቃድ ለጣልያን መንግሥት እንዲሰጡ፤

ለ/ ከእነዚህ ከተጠቀሱት አውራጃዎች ሌላ፤ በተቀሩት የኢትዮጵያ ግዛቶች ውስጥ ለውጭ አገር መንግሥታት የሚመደቡት የልማት ሥራዎች ሁሉ፤ ቅድሚያው ለጣልያን እንዲሰጥ፤

ሐ/ አሁን ያለውን የንጉሡን አስተዳደር ለማሻሻል ከሊግ ኦፍ ኔሽን የሚደረገው እርዳታ ሁሉ የሚከናወነው በጣልያን መንግሥት ቁጥጥር ሥር እንዲሆን፤ በብዙ ድካም የአስቸጋሪውን የኤደንን ስምምነት አግኝቼ የተዘጋጀውን የዕርቅ ፕላን መንግሥትዎ ሳይቀበለው በመቅረቱ ቅሬታ አድሮብኛል።

## 2ኛ. እ.ኤ.አ መስከረም 18 ቀን 1935 ዓ.ም፤

በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው ጠብ፤ የሰላም መፍትሔ እንዲያገኝ የመንግሥታት ማህበር ያቋቋመው የአምስት አገሮች ኮሚቴ አጥንቶ ያቀረበውን ሐሳብ፤ እንኳንስ ለመቀበል በጉዳዩ ላይ ለመነጋገር እንኳን መንግሥትዎ ባለመፍቀዱ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት በመሰለው እንዲወስን፤ ከፍ ያለ ዕድል አግኝቶ ነበር።

ነገር ግን መንግሥትዎ የፈረንሣይ ሙሉ ድጋፍ ስላልተለየው፤ ምንም ዓይነት የሚጐዳ እርምጃ አልተወሰደበትም። ይልቁንም በዚህ በአምስቱ አገሮች ኮሚቴ ውስጥ ፈረንሣይ አባል ሆና በመገኘት ባደረገችው ተጽዕኖ፤ በጣልያን አቋም ላይ በመፍረድ ፋንታ፤ ለጣልያን የሚጠቅም ውሳኔ ሲደረግ፤ እንደ ትልቅ ድል ሆኖ መቆጠር ነበረበት። መንግሥትዎም፤ ይህን የቀረበለትን ሐሳብ አልቀበልም ብሎ በሩን ከመዝጋቱ በፊት፤ በጉዳዩ ላይ ስለተደረገው ጥናት ለማወቅ ማብራሪያዎችን ቢጠይቅ ኖሮ፤ በፈረንሣይ ጥረት ሊግ ኦፍ ኔሽን ያደረገው እርዳታ ምን ያህል ጠቃሚ መሆኑን በይበልጥ ለመገንዘብ ይችል ነበር። ስለዚህ፤ መንግሥትዎ ይህን የቀረበለትን የዕርቅ ሐሳብ በሚገባ ሳይመረምርና ውይይትም ሳያደርግበት አልቀበልም በማለቱ፤ ምን ያህል እንደጐዳውና እኔንም ምን ያህል እንዳሳዘነኝ ሳልገልጽልዎ ማለፍ አልፈልግም።

---

* ላቫል ለሙሶሊኒ የላከው የጉዛዜ ደብዳቤ እ.ኤ.አ ታህሣሥ 22 ቀን 1935 ዓ.ም

## 3ኛ. እ.ኤ.አ ጥቅምት 1935 ዓ.ም፤

የጣልያን ጦር ኃይል ወደ ኢትዮጵያ ግዛት ዘልቆ አገሩን በጦርነት መያዝ ላይ መሆኑ ከተረጋገጠ በኋላ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን አንቀጽ 16 በሚጠይቀው መሠረት የጠነከረ ውሳኔ ቢያደርግ፤ በመንግሥትዎ ላይ የሚወድቀው ችግር እጅግ የከበደ ይሆን እንደነበረ ያስታውሱታል። በዚህ ጊዜ እኔ ራሴ ዤኔቭ ተገኝቼ እጅግ አስቸጋሪዎች የሆኑትን የእንግሊዝንና የሌሎቹንም አገሮች መልዕክተኞች አግባብቼ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን ለጊዜው እንደ ነዳጅ ዘይት የመሳሰሉትን ጉዳት ሊያደርሱብዎ የሚችሉትን የኤኮኖሚ ዕገዳዎች በመንግሥትዎ ላይ እንዳይወስን አስደርጌያለሁ። ይህንንም ያደረግሁት በሁለቱ አገሮቻችን መካከል የተሳሰረውን ወዳጅነት በመመርኰዝ ብቻ ሳይሆን፤ እንደዚሁም የአውሮፓንም ሰላም ለመጠበቅ በማሰብ ነው።

## 4ኛ. እ.ኤ.አ ታህሣሥ 16 ቀን 1935 ዓ.ም፤

ከታላቋ ብሪታኒያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ከሚስተር ሳሙኤል ሖር ጋር መልካም ግንኙነት በመዘርጋት፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የሚካሔደውን ጦርነት ወደ ሰላም ለመለወጥ፤ ከዚህ ቀደም ያልታሰበውን ለመንግሥትዎ እጅግ ጠቃሚ የሆነውን የዕርቅ ፕላን በሕብረት ለማዘጋጀት በመቻላችን ከፍ ያለ ተስፋና ደስታ አድሮብኝ ነበር። **ይህንንም "ላቫል ሖር" የተሰኘውን ፕላን፤** *መንግሥትዎ* ያለ አንዳች ማመንታት መስማማቱንና ለሰላም ዝግጁነቱን በፍጥነት እንዲያስታውቅ፤ እያከታተልኩ የላኩልዎትን መልዕክቶች ሳይቀበሉ በመቅረትዎ እጅግ አድርጌ አዝኛለሁ። በጠቅላላው በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ለተፈጠረው ግጭት እስከዛሬ ድረስ በልዩ ልዩ ጉዳና ለመንግሥትዎ ጠቃሚ የሆነ የሰላም መፍትሔ እንዲገኝ ያደረግኳቸውን ጥረቶች ሁሉ፤ ግምት ሰጥተው በመልካም መንፈስ የተመለከቱት መስሎ ስላልታየኝ፤ ያደረብኝን ቅሬታ ልደብቅዎ አልፈልግም። ሆኖም፤ አገርዎ ለገጠማት ችግር መልካም መፍትሔ የሚያስገኝላት በሰላም መንገድ በመደራደር ስለሆነ፤ ወደፊት አንዳንድ የዕርቅ ሐሳቦች ቢቀርቡልዎ፤ ከመጀመሪያው ፊት ሳይነሡ እንዲመረምሯቸው አሳስብዎታለሁ።

ክቡር ዱቼ፤ ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን የወዳጄን ስሜት ከተረዳ በኋላ በሰጠው መልስ፤ ላቫል እንደተመኘው « ... **ወዳጅነታችንን በመመርኰዝ ለጣልያን ያሰብከውና የለፋኸው ሁሉ ጥሩ ሊሆን ያልተጠቀምኩበት እኔ ነኝ** ... » ብሎ ይቅርታ አልጠየቀውም። ይልቁንም ሙሴ ላቫል በብዙ ድካም ያስገኘኋቸውን ውሳኔዎች ባለመቀበልዎ አዝናለሁ ብሎ የዘረዘራቸው ጉዳዮች ሁሉ፤ የጣልያንን ትክክለኛ ዓላማና ፍላጎት ያላሟሉ በመሆናቸው ነው የሚል አስተያየት ከመግለጽ አልተቆጠበም። ለዚህም በሰጠው ማብራሪያ፤ **የቀረቡለት የዕርቅ ሐሳቦች ሁሉም በአንድ መልክ የሚያተኩሩት፤ ጣልያን በኢትዮጵያ የሚኖራትን መብት በኤኮኖሚ ልማት ላይ ብቻ ስለሚወስናት፤ የፋሽስቱን መንግሥት ሊያረካ አልቻለም** ብሏል። በሙሶሊኒ አስተያየት ከቀረቡለት ልዩ ልዩ የዕርቅ መፍትሔዎች ውስጥ፤ በመጠኑም ቢሆን ድርድር ለማድረግ ዕድል የሚሰጠው፤ **በላቫልና በሖር ስም** ተሠይሞ የቀረበው ፕላን ነበር። እሱንም ትልቁ የፋሽስት ምክር ቤት ለማጥናት በሚዘጋጅበት ሰዓት፤ የኢትዮጵያ ንጉሥ ቀድመው አልቀበልም በማለታቸውና ወዲያውም የፕላኑ ተባባሪ አዘጋጅ የሆነው የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር

ሳሙኤል ሖር፤ በፓርላማው በተነሳበት ተቃውሞ ምክንያት ሥልጣኑን በመልቀቁ፤ እንዳች እርምጃ ሳይወሰድበት ባዶ ሆኖ ቀርቷል ብሏል።

እዚህ ላይ፤ በፋሽስቱ መሪ አቋምና በተለያዩት አስታራቂዎች መካከል ያለውን መሠረታዊ የሆነ የሐሳብ ልዩነት ደህና አድርጐ መመልከት ያስፈልጋል። እንደሚታወሰው፤ ከአንድም ሁለት ሦስት ጊዜ፤ ከአስታራቂዎች በኩል የቀረበው ሐሳብ፤ « ... **የኢትዮጵያ ነፃነት የተጠበቀ ሆኖ፤ ከግዛቶቿ ውስጥ አንዳንዶቹን አውራጃዎች ለጣልያን መንግሥት በበጐ ፈቃድ እንድታስረክብና፤ በሌሎቹም ግዛቶቿ ውስጥ በውጭ አገሮች ለሚደረጉት የኢኮኖሚ ልማቶች ሁሉ፤ ቅድሚያውን ለጣልያን እንድትሰጥ** ... » የሚል ነው። ከዚህም በላይ፤ የኢትዮጵያ መንግሥት አስተዳደሩን ለማሻሻል እንዲችል ከሊግ ኦፍ ኔሽን የሚሰጠውን እርዳታ በተግባር የማዋል ሥልጣን የሚኖረው፤ የጣልያን መንግሥት እንዲሆን የቀረበ ሐሳብ መኖሩ አይረሳም። የፋሽስቱ መንግሥት ግን እነዚህን ሁሉ ሐሳቦች አልተቀበለም።

ግልጽና ቀጥታ በሆነ አነጋገር ለማስረዳት፤ ገና ከጠዋቱ ሙሶሊኒ ቆርጦ የተነሣውና ጦርነት የጀመረው፤ የኢትዮጵያ ነፃነት እንደ ተጠበቀ ሆኖ፤ ከግዛቶቿ የተወሰኑ አውራጃዎችን በስጦታ መልክ ለመቀበልና በሌሎቹም በንጉሠ ነገሥቱ ሥልጣን ውስጥ በሚተዳደሩት አውራጃዎች፤ የኢኮኖሚ ልማት ሥራ አስኪያጅ ለመሆን አይደለም። ሙሶሊኒ፤ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል አጥቅቶ ወረራውን በጀመረ ጊዜ፤ ትክክለኛ ዓላማውና ግቡ ምን እንደሆነ አልደበቀም። ይኸውም፡-

**1ኛ/ የአድዋን ብድር ለመመለስና በምኒልክ የተዋረደውን የጣልያንን ታሪክ ለማደስ፤**

**2ኛ/ መላ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ አድርጐ በመያዝ፤ የአገሪቱን የተፈጥሮ ሀብት ለማልማትና የጣልያንን ሕዝብ የኑሮ ደረጃ ለማሻሻል፤ መሆኑን በግልጽ አስረድቷል።**

በዚህ መነሻና ግብ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የጦርነቱ እሳት ከተቀጣጠለ በኋላ፤ የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ፒየር ላቫል፤ ከአንድም ሁለት ጊዜ አስታራቂ እሆናለሁ ብሎ ሲሯሯጥ የታየው፤ በፖለቲካ ታዛቢዎች ዘንድ እንዲሁ ለማስመሰል ነው እንጂ፤ የሙሶሊኒ ፍላጐት ምን እንደሆነ ከእሱ የበለጠ የሚያውቅ ሰው አልነበረም። የወልወል ግጭት ከደረሰ ከሦስት ሳምንታት በኋላ፤ ሮም ሔዶ በኢትዮጵያ ጉዳይ ከሙሶሊኒ ጋር ያደረገው ስምምነት፤ ተሰውሮ የሚኖር አይደለም። እርግጥ ነው ! በዚያን ጊዜ ሙሶሊኒ በነበረው የጦር ሠራዊት ብዛትና የአየር ኃይል ድርጅት፤ ኢትዮጵያን በጥቂት ቀናት ውስጥ ጠቅልሎ መያዝ እንደሚችል ላቫል ስለአመነበት፤ በፈረንሣይ መንግሥት ስም ሆኖ ለዲክታተሩ መሪ የሰጠው " ነፃ እጅ " (Main Libre) የተባለው ድጋፍ አደባባይ ወጥቶ የሚጋለጥበት ዕድል አይደርስም ብሎ አስቦ ነበር። ኋላ ግን ጦርነቱ እንደተጀመረ ሒደቱን ሲመለከተው፤ ለካስ ኢትዮጵያን በቀላሉ መያዝ አይቻልም ኖሮዋል ? በማለት እጅግ አዘነ። የኢትዮጵያም የነፃነት ተከላካይነት እየበረታ በሔደ ቁጥር፤ የሮሙም የምስጢር ስምምነት ሳይጋለጥ የመኖር ዕድሜው እንደሚያጥር ስለተረዳው፤ የማያቋርጥ ዕንቅልፍ የሚነሣ ጭንቅ አደረበት። ይኸውም የመጀመሪያው፤

ሙሶሊኒ የሮሙን ምሥጢር ይፋ አድርጐ እንዳያዋርደው፣ የሚጠይቀውን ሁሉ ከመፈጸም አለመቦዘን ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ሽንጐ የፋሽስቱ መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ስለሚፈጽመው ግፍ ከአባል አገሮች ጋር ተሰልፎ ከማውገዝ ለማምለጥ የሚችልበትን መንገድ ማግኘት ነበር።

የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ከሆነበት ከሰኔ 1935 እስከ ጥር 1936 ዓ.ም ድረስ ባሉት የሰባት ወራት ዕድሜ ውስጥ፣ የጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ልብስ ፓሪስ እየተወ፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነቱን ቦርሳ እየያዘ በገኔቭ የሊግ ኦፍ ኔሽን ስብሰባ ላይ ባለማቋረጥ ይካፈል የነበረበት ዋናው ምክንያት፣ ከዱቼ ጋር ያደረገው የሮም የምሥጢር ስምምነት፣ በአንድ ምክንያት እንዳያፈተልክና ውርደት እንዳይደርስበት ለመከላከል መሆኑ ታውቋል። በሊግ ኦፍ ኔሽን የሙሶሊኒ ዋና መልዕክተኛ የሆነው ፖምፔዎ ባሮን አሎይዚ፣ በአገሩ ፕሮቶኮል የምክትል ሚኒስትርነት ደረጃ እንኳ አልነበረውም። ነገር ግን ከፈረንሣይ ዋና መልዕክተኛ ጋር ለመነጋገር ቀጠሮ ሲጠይቅ፣ ብዙ ጊዜ አሎይዚ ቢሮ ድረስ እየሮጠ ሲሔድ የታየው፣ የጠቅላይ ሚኒስትርነትን ሥልጣን የተሸከመው ራሱ ፒየር ላቫል ነበር። አንዳንድ ጊዜም በሊጉ ስብሰባ ላይ የኢትዮጵያና የጣልያን ጉዳይ ሲነሣ፣ ላቫል የሚሰጠው ድጋፍ በቂ ሳይሆን ቀርቶ ክቡር ዱቼ መቆጣቱ የተሰማ እንደሆነ፣ በአማላጅነት የሚያገለግለው ባሮን አሎይዚ ስለሆነ፣ እሱን ተንከባክቦ መያዝ ጠቃሚ ነው ብሎ በማመን ክብሩን አለመጠበቁ ታይቶበታል። ፖምፔዎ አሎይዚም፣ ለጌታው ለክቡር ዱቼ በየዕለቱ በሚያስተላልፈው ራፖር፣ « ... ዛሬ ላቫልን ጠርቼ በዚህ ... በዚህ ... ጉዳይ ላይ ድጋፉን እንዲሰጠን ጠይቄዋለሁ። ... ትናንት ፓሪስ ለላቫል ስልክ ደውዬ በአንዳንዶቹ ጉዳዮቻችን ላይ እንዲረዳን በዝርዝር አስረድቼዋለሁ ... » እያለ ሲንደላቀቅ፣ እንኳንስ ከአንድ ጠቅላይ ሚኒስትር ከረዳቱም ጋር ቢሆን እስከዚህ እየተዳፈረ የሚነጋገር አይመስልም ነበር።

ለብዙዎቹ የፖለቲካ ታዛቢዎች እጅግ አስገራሚ ሆኖ የታየው፣ ላቫል የፈረንሣይን መንግሥት እያዋረደ ለሙሶሊኒ እንደዚያ ሲታዘዝ፣ ዱቼ በበኩሉ ከላቫል የሚያገኘውን እርዳታ በቁም ነገር ሲመለከተው አለመታየቱ ነው። የቀረው ቢቀር ሊግ ኦፍ ኔሽን በፋሽስቱ መንግሥት ላይ የኤኮኖሚ ዕገዳ ሲወስን፣ በዝርዝሩ ውስጥ የነዳጅ ዘይት እንዳይጨመር ያስደረገለት ላቫል መሆኑን መርሳት አልነበረበትም። የፋሽስቱ መሪ ራሱ፣ « ... ሊግ ኦፍ ኔሽን የነዳጅ ዘይት ዕገዳ እንዲደረግ ከወሰነብኝ፣ የጀመርኩትን ጦርነት አቁሜ የሰላም ንግግር ለማድረግ እገደዳለሁ ... » እስከ ማለት ደርሶ እንደነበረ፣ ባሮን አሎይዚ በማስታወሻው ላይ የገለጸው ይታወሳል። በዚህ አኳኋን፣ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር ኢትዮጵያን እየጐዳ ለፋሽስት መንግሥት ያደረገው እርዳታ፣ ወደር የማይገኝለት መሆኑን ለመገንዘብ አያዳግትም።

ፒየር ላቫል የመጨረሻው ታሪኩ ደህና አድርጐ እንዳሳየው፣ እንኳንስ ፍጹም ባዕድ ለሆነችው ለኢትዮጵያ ይቅርና፣ ለወለደችው ለእናቱ ለፈረንሣይም ያልቆመ ጨካኝና ከዳተኛ መሆኑን ያስመሰከረ ነው። ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር ተሰልፎ ለአውሮፓ ሰላም ጠንቅ ከሚሆን፣ የኢትዮጵያን ነፃነት መሠዋት ያስፈልጋል ብሎ በገኔቭ ያንን ሁሉ አሳዛኝ ሥራ ሲፈጽም ከቆየ ከአራት ዓመታት በኋላ፣ በገዛ አገሩና በወገኖቹ በፈረንሣዮች ላይ ያደረሰው በደል፣ ከዚህ ቀደም ታይቶ የማይታወቅ ሆነ። እ.ኤ.አ በ1940 ዓ.ም በናዚስቶችና እንዲሁም በፋሽስቶች ጦር ኃይል ፈረንሣይ ተሸንፋ ከተያዘች በኋላ፣ በሂትለር ፈቃድ "ቪሺ" በተባለው

አውራጃ ላይ በተቋቋመው የፈረንሣይ የተወሰነ ክልል አስተዳደር፣ የምክትል ፕሬዚዳንትነት ሥልጣን አግኝቶ ለናዚ መንግሥት ደጋፊነቱንና ታማኝነቱን ለማሳየት ብዙ ጥረት አደረገ። በዚያን ጊዜ የዚሁ የቪሺ አስተዳደር ፕሬዚዳንት የሆነው ማርሻል ፊሊፕ ፔተን (Philippe Petain) ላቫል ከናዚስቶች ጋር የሚያደርገው ማጨብጨብ በጣም ስለአሠጋው፣ ከሥልጣን እንዲነሣ እርምጃ ወሰደበት። ነገር ግን፣ በቪሺ ለተቋቋመው የፈረንሣይ የክልል አስተዳደር የበላይ መሪ የሆነው አዶልፍ ሂትለር፣ ማርሻል ፔተን በወሰደው እርምጃ በጣም ስለተቆጣ፣ የባሰ ይባስ ብሎ ከምክትል ፕሬዚዳንትነት ይልቅ በጠቅላይ ሚኒስትርነት ደረጃ የአስተዳደሩ ሙሉ ሥልጣን እንዲሰጠው አደረገ። ጀርመን ተሸንፎ ፈረንሣይ ነፃነቷን እስከአገኘችበት ጊዜ ድረስ፣ ፒየር ላቫል በሥልጣን በቆየባቸው በሐያ አራት ወራት ውስጥ፣ " ድል የሂትለር ነው " የሚል መፈክር አውጥቶ፣ ፩ኛ/ በአገር ፍቅር ስሜት ተነሣስተው ከጀርመን ጋር ለመዋጋት የሚዘጋጁትን ወገኖቹን ፈረንሣዮች እያስያዘ በማስገደል፣ ፪ኛ/ የአይሁዳዊ ደም ያላቸውን ፈረንሣዮች በሙብራት እያስለቀመ ናዚስቶቹ እንዲጨርሷቸው በማስረከብ፣ የፈጸማቸው የጭካኔ ሥራዎች ተዘርዝረው አያልቁም።

ፒየር ላቫል በፖለቲካ ሕይወቱ፣ አገሩንና ወገኖቹን ከድቶ ይህን ሁሉ አሳፋሪና አሳዛኝ ተግባር ሲፈጽም፣ አንድ ቀን ፈረንሣይና የአውሮፓ አገሮች ከናዚስቶችና ከፋሽስቶች ተላቀው የነፃነት ፀሐይ በሚወጣላቸው ጊዜ፣ የሠራውን የግፍ ዕዳ መክፈል እንዳለበት አላሰበበትም። እ.ኤ.አ በ1935 ዓ.ም የሙሶሊኒ ዋና ወዳጅ ሆኖ የኢትዮጵያ ነፃነት እንዲገፈፍ ያደረገው ጥረት፣ ፋሽስትና ናዚ አንድ ሆነው ለአውሮፖ ሰላም ጠንቅ እንዳይሆኑ ነው የሚል ምክንያት ይሰጥ እንደነበረ ይታወሳል። ነገር ግን ከአራት ዓመታት በኋላ፣ ሂትለርና ሙሶሊኒ አንድነት ገጥመው የፈረንሣይንና የአውሮፓን አገሮች በጦር ሲወጉ፣ ላቫል ለአገሩ ለፈረንሣይ እንኳ መቆም ሳይችል የዲክታተሮቹ ታማኝ አገልጋይ መሆንና ወገኖቹን መጉዳት ይጠቅመኛል ብሎ ከሀዲነቱን በገሀድ ሲፈጽም ተገኘ።

በኢትዮጵያችን አንድ የሚነገር ምሳሌ አለ። ይኸውም፣ በሰፈሩት ቁና መስፈር አይቀርም የሚባለው ነው። ሂትለርና ሙሶሊኒ ድል ሆነው፣ የአውሮፓውያን ነፃነት ሲመለስ፣ ላቫል ያንን ሁሉ ግፍ ሲያከናውን ከነበረበት ከቪሺ ግዛት ጠፍቶ ወጥቶ መጀመሪያ በአስትሪያ፣ ከዚያም በስፔን፣ እንደገናም ወደ ኦስትሪያ ተመልሶ እየተንከራተተ ተደብቆ ለመኖር ሲጥር፣ የአሜሪካ የጦር ሹማምንቶች እጁን ይዘው ነፃነቷን ላስመለሰችው ለፈረንሣይ አስረከቡት። በዚያን ጊዜ በጀኔራል ሻርል ደጎል የሚመራው የፈረንሣይ ጊዜያዊ መንግሥት፣ ፒየር ላቫልን ለፍትሕ አቅርቦ በጥይት ተደብድቦ እንዲሞት ከተፈረደበት በኋላ፣ ቅጣቱን ለመቀበል እንዲሰናዳ በተጠየቀበት ሰዓት፣ ያለጥርጥር ሙሴ ላቫል፣ "ድል ለዘለዓለሙ የሂትለር ነው" እያለ እንደፎከረው ሁሉ፣ በውኑ ድል የሂትለር ሳይሆን መቅረቱን በዚያች በመጨረሻይቱ የሕይወቱ ትንፋሽ ላይ ተረድቶት ሳይጸጸተው አልቀረም።

እንግዲህ ! በገዛ አገራቸው በገዛ ቤታቸው ያንን ሁሉ ሥቃይ የተቀበሉት ፈረንሣዮች ትክክለኛውን ፍርድ አግኝተዋል። ኢትዮጵያም ቀደም ሲል ለደረሰባት በደል፣ በዚህ አጋጣሚ ፈጣሪዋ ተገቢውን ፍርድ እንድታገኝ ዕድሉን አልነፈጋትም።

# ምዕራፍ ፲

## ንጉሠ ነገሥቱ በማይጨው ግንባር*

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በደሴ ከተማ "መርሖ" ተብሎ በተሠየመው ቤተመንግሥት ጠቅላይ የጦር መምሪያቸውን አቋቁመው ለሁለት ወራት ያህል ሲሠሩ ከቆዩ በኋላ፣ በሰሜንና በደቡብ ኢትዮጵያ ተሰልፈው ከጠላት ጋር ከሚዋጉት የጦር አለቆች የሚደርሷቸው ዜናዎች ሁሉ፣ ከዕለት ወደ ዕለት አብዛኛዎቹ እጅግ የሚያሳዝኑና ተስፋም ወደ መቁረጥ የሚገፋፉ ሆኑ። ከእነዚህም መካከል ዋና ዋናዎቹ የሚከተሉት ነበሩ።

እንደ ኢት/አቆ ጥር 19 ቀን 1928 ዓ.ም በመጀመሪያ የደረሳቸው አስከፊ ዜና፣ በምዕራብ ኦጋዴን በኩል ተሰልፎ፣ ጠላትን የገጠመው የራስ ደስታ ዳምጠው ጦር ድል መሆኑን ነው። የንጉሠ ነገሥቱ አማችና የሲዳሞ ጠቅላይ ገዥ የሆኑት ራስ ደስታ ዳምጠው፣ በምዕራብ ኦጋዴን ያላቸውን ጦር እየመሩ ጠላትን በማስጨነቅ የጣሊያን ሱማሌ ግዛት ወሰን ከሆነው "ዶሎ" እስከተባለው ሥፍራ ለመዝለቅ ችለው ነበር። ነገር ግን፣ ሱማሌ ላይ የሰፈረው የፋሽስት ጦር አዛዥ ጄኔራል ግራሲያኒ በደረሰው መረጃ መሠረት፣ በንብ ጣዮችና መርዝ ነስናሾች የሆኑትን አውሮፕላኖችና እንዲሁም ቁጥራቸው በርከት ያሉ መድፍ የጫኑ ታንኮችን አዘጋጅቶ ስለጠበቀ፣ የራስ ደስታ ጦር ዶሎ ሲደርስ፣ ያላሰበው ብርቱ ጥቃት ደረሰበት። በዚሁ ውጊያ ላይ ከኢትዮጵያ በኩል ሰባት ሺህ ሠራዊት ሲያልቅ፣ አሥር ሺህ የሚሆነው ደግሞ በብርቱ ቆሰለ። የጦሩ መሪ ራስ ደስታም ከሞት የተረፉትን ጥቂቶች ወታደሮቻቸውን ይዘው፣ ወደ ሲዳሞ ግዛታቸው መመለስና ሌላ ዝግጅት ማድረግ ግዴታ ሆነባቸው። ንጉሠ ነገሥቱም በመርሖ ቤተመንግሥት በምክር እንዲረዷቸው አቆይተዋቸው የነበሩት፣ የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ደጃዝማች ገብረማርያም ጋሪ በአስቸኳይ ወደ ሲዳሞ ሄደው፣ ራስ ደስታን እንዲረዷቸው አደረጉ። ደጃዝማች ገብረማርያም በሲዳሞ ሕዝብ ዘንድ የታወቁ በመሆናቸው፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ለሲዳሞ ሕዝብ የተላከውን አዋጅ እያስነገሩ፣ ጠላትን ለመከላከል የሚያስችል ጦር ለማዘጋጀት ብርቱ ጥረት አድርገው ነበር። ከራስ ደስታ ጋር ሆነው በልዩ ልዩ ቦታዎች እየተዘዋወሩ አንድ ዓመት ያህል በአርበኝነት ሲዋጉ ከቆዩ በኋላ፣ ደጃዝማች ገብረማርያም በጦሩ ሜዳ ላይ በጀግንነት ሲሞቱ፣ ራስ ደስታም ብዙ ተጋድሎ ካደረጉ በኋላ እጃቸው በፋሽስት ተይዞ በግፍ ተገደሉ።

በሰሜን ግንባር፣ በአባ ራስ ሙሉጌታ፣ በተምቤን ራስ ሥዩም፣ በሽሬ ራስ እምሩ፣ የፋሽስት አየር ኃይል እንደ ዝናብ የሚያወርድባቸውን ቦንብና የሚረጭባቸውን የጋዝ መርዝ፣ በምድር ጦርም በታንክና በዘመናዊ መድፍ እየተደገፈ የሚያጠቃቸውን ሠራዊት መመከት ብቻ ሳይሆን፣ አልፎ አልፎም ድል እየመቱ ጠላትን በማጥቃት የሚያስደስት ጀግንነት ፈጽመው ነበር። ነገር ግን፣ የፋሽስት ኃይል በምድርም ሆነ በአየር ከዕለት ወደ ዕለት እየጨመረና እየሰፋ

---

* ገብረወልድ እንግዳወርቅ የማይጨው ታሪክ

በመምጣቱ፤ ወደፊት በመግፋት ፋንታ ወደ ኋላ ማፈግፈግ ግዴታ ሆነባቸው። እንደሚታወሰው፤ ሙሶሊኒ የአድዋ ውርደት እንዳይደገምበት ኢትዮጵያን ለመውጋት ያዘጋጀው ጦር፤ በብዛቱም ሆነ በመሣሪያዎቹ ድርጅት ተወዳዳሪ የሌለው ስለሆነ፤ የኢትዮጵያ የመከላከያ ኃይል ከተወሰነ ጊዜ የበለጠ ውጊያውን ለመቀጠል እንደማይችል፤ ገና ከመነሻው የታወቀ ነበር። የሙሶሊኒ ጦር አዛዥ ጄኔራል ባዶግሊዮም ኢትዮጵያን ለመያዝ፤ በዓለም ሕግ የተከለከለውን የጋዝ ጢስና መርዝ በብዛት እየረጨ ሕዝቡን ከመጨረስ በስተቀር፤ በምድር ጦርና በአየር ኃይል ብቻ በአጭር ጊዜ ውስጥ ድል ማግኘት እንደማይችል አመነበት። በዚህ መሠረት በመቶ የሚቆጠሩት የጋዝ ጢስና መርዝ የሚረጩት የፋሽስት አውሮፕላኖች፤ በጦር ሜዳ በሚዋጋው ሠራዊት ላይ ብቻ ሳይሆን፤ በገበያና በቤተክርስቲያን በሚሰበሰበው ሰላማዊው ሕዝብ ላይ ጭምር ስለሆነ፤ የደረሰው ጉዳት በቀላሉ የሚነገር አልሆነም።

በአላጌ፤ በተምቤንና በሽሬ የተሰለፈው የኢትዮጵያ ሠራዊት፤ ከመቶ ዘጠናው የሚጠቀምበት መሣሪያ፤ ከአርባ ዓመታት በፊት በነበሩት የውኀሮግራና የስናይደር ጠበንጃዎች ሲሆን፤ መውዜርና መትረየስ ያነገቡት ተዋጊዎች ቁጥራቸው ከመቶ አሥር እንደማይደርሱ ታውቋል። ይሁን እንጂ፤ የሙሶሊኒ ጦር የዓለምን ሕግ በመጣስ የመርዝ ጢስና ጋዝ እየረጨ ሕዝቡን መፍጀት ሳይሆን፤ በምድር ጦር በታንክና በዘመናዊው መድፍ፤ ከዚያም በላይ በአውሮፕላን በንብ በመጣል ብቻ የተወሰነ ቢሆን ኖሮ፤ መላ ኢትዮጵያን ለመያዝ የዓመታት ጊዜ እንደሚወስድበት አይጠረጠርም ነበር። ይህም አስተያየት ትክክል መሆኑን ለመገመት የሚያስችለው፤ በሰሜን ሆነ በደቡብ ግዛት፤ በየግንባሩ የተሰለፈው የኢትዮጵያ ሠራዊት፤ ጠላት ከታጠቃቸው ዘመናዊ መሣሪያዎች ውስጥ አንድ በመቶ እንኳን ሳይኖረው (1%) አብዛኛውን ጊዜ በወጨፎና በጉራዴ እየተዋጋ ያስመሰከራቸው የጀግንነት ሥራዎች ናቸው።

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ በሰሜን ኢትዮጵያ ልዩ ልዩ ግንባር ላይ የተሰለፉት አዝማቾች፤ ለአራት ወራት ባላቸው አቅም ሁሉ ሌት ተቀን ሲዋጉ ከቆዩ በኋላ፤ የጠላት ጦር በታንክና በመድፍ ካለው ከፍተኛ መሣሪያ ሌላ በአውሮፕላን በሚረጨው መርዝ ሕዝቡን ስለጨረሰባቸው፤ ሁሉም ወደኋላ መመለስ ግዴታ ሆኖባቸዋል። እንደዚሁም፤ ከመሣሪያዎች እጥረት ሌላ በየጦሩ ግንባር የደረሱት አንዳንድ ያልተጠበቁ ችግሮች፤ ለጠላት ድል አድራጊነት ምን ያህል ዕድል እንደሰጡ መገንዘብ ይቻላል።

- በሽሬ ግንባር ለመዝመት ከጉጃም የመጡት ደጃዝማች ገሠሠ በለውና ግብረአበሮቻቸው፤ ከጠላት ጋር በመላላክ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩትን ዘማቾች አስከትለው በመክዳታቸው፤ ራስ እምሩ በሚመሩት ጦር ላይ ከፍ ያለ ጉዳት አድርሰዋል። ሆኖም እምሩ ኃይለሥላሴ በዚህ በደረሰው አሳዛኝ ሁኔታ ሳይሸበሩና ሳይበሳጩ፤ ቀሪውን ጦራቸውን አስተባብረው በትዕግሥትና በዘዴ እየመሩ፤ እስከሚቻላቸው ድረስ ጠላትን በማጥቃት ያሳዩትን ጀግንነት፤ የፋሽስቱም ፕሮፓጋንዳ ሳይቀር አድናቆቱን አልነፈጋቸውም።

- የሰሜን ጦር ጠቅላይ አበጋዝ (ዋና መሪ) የሆኑት ራስ ካሣ ኃይሉና የተምቤን ዋና አዝማች ራስ ሥዩም መንገሻ፤ ጠላት በአየር ኃይልና

በምድር ጦር በሰፊው ተዘጋጅቶ ሊያጠቃቸው በመገሥገስ ላይ መሆኑን ንጉሠ ነገሥቱ ሲሰሙ፣ አሳጌ ላይ ከሠፈረው ራስ ሙሉጌታ ይገዙ ከሚመሩት ጦር፣ ደጃዝማች መሸሻ ወልዴና ደጃዝማች መንገሻ ይልማ (የቀ.ኃ.ሥ የወንድም ልጅ) ደጃዝማች በየነ ወንድም አገኘሁና ፊታውራሪ ዘውዱ አባኮራን፣ ከነሠራዊታቸው ወደ እነ ራስ ካሣ ለእርዳታ በአስቸኳይ እንዲሄዱ ትዕዛዝ አስተላለፉ። ነገር ግን፣ ንጉሠ ነገሥቱ በራዲዮ መገናኛ ከየግንባሩ የሚደርሳቸውን ራፖርና እሳቸውም የሚሰጡትን መምሪያ፣ የጠላት ምሥጢራዊ ድርጅት እየጠለፈ በመስማት የማጥቃት ዝግጅቱንና ፕሮግራሙን በቅድሚያ ማስተካከል ስለቻለ፣ ለኢትዮጵያ ሠራዊትና ለመሪዎቹ ከፍ ያለ አደጋ ሆነ። በዚህም መሠረት፣ የራስ ሙሉጌታ ጦር ተቀንሶ ወደ ተምቤን እንዲዛወር መታዘዙን ማርሻል ባዶግሊዮ እንደዐወቀ፣ በሰሜን በኩል በሦስት ግንባር በተሰለፈው የኢትዮጵያ ሠራዊት ላይ በአየር ኃይል መጠን የሌለው ቦንብ በመጣልና በምድር ጦር በማጥቃት ከባድ ጉዳት አደረሰበት።

- የታወቁት የአድዋው ስመጥር ጀግና ራስ ሙሉጌታ ይገዙ፣ "አምባራዶም" ላይ ለሦስት ቀናት በብርቱ ከተዋጉ በኋላ፣ ጠላት በአውሮፕላን የሚያዘንብባቸውን መርዝና የጋዝ ጢስ ለመቋቋም ባለመቻላቸው፣ ወደኋላ ተመልሰው ንጉሠ ነገሥቱ ወደ አሉበት መጥተው ለመቀላቀል ጉዞ ጀምረው ነበር። ነገር ግን፣ ፋሽስቶች ውስጥ ዐዋቂ እየላኩ የራያና አዘቦ ተወላጆችን በገንዘብና በፕሮፓጋንዳ አታለዋቸው ስለነበረ፣ የካቲት 18 ቀን 1928 ዓ.ም ራስ ሙሉጌታ በሚጓዙበት "አህዮ" በተባለው ሥፍራ ባልታሰበ ሰዓት አድፍጠው በጥይት ገደሏቸው። እንደዚሁም፣ የወለጋው ጦር አዝማች ቢትወደድ መኰንን ደምሰው፣ ቀደም ሲል የጦር ሚኒስትሩ "አምባራዶም" ላይ የገጠማቸውን ችግር ሰምተው ለእርዳታ ለመድረስ ሲገሠግሱ፣ "ቀይሐታ" በተባለው ቦታ የጠላት ጦር ደርሶባቸው፣ ለሁለት ቀናት ባለማቋረጥ በጀግንነት ከተዋጉና የጠላትም ጦር መሸሽ ከጀመረ በኋላ፣ በአውሮፕላን የሚጣለው ቦንብ ወድቆባቸው ሕይወታቸው አለፈ።

- በሽሬ ግንባር ስለነበረው የኢትዮጵያ ጦር ብዙዎቹ የፋሽስት ባለሥልጣኖች በታሪክ ማስታወሻቸው ላይ እንደገለጹት፣ ዋናው አዝማች ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ ያሳዩት የውጊያ ዘዴ፣ ማርሻል ባዶግሊዮን እጅግ አሳስቦት እንደነበረ ተናግረዋል። ስለዚህም፣ በሽሬ ግንባር ያለውን የኢትዮጵያን ጦር ለመደምሰስ በታንክና በመድፍ ከማጥቃት ይልቅ፣ በአውሮፕላን የሚረጨው መርዝ ሠራዊቱን ሊበታትነው ይችላል በማለት፣ ባዶግሊዮ በመጨረሻ በወሰደው እርምጃ፣ የራስ እምሩን ጦር ወደ ኋላ እንዲያፈገፍግ አስገድዶታል። ራስ እምሩም፣ ሠራዊታቸው በመርዝና በጋዝ ስለተጐዳባቸውና ወደፊት መግፋት ስላልቻሉ፣ ጥቂቶች የተረፉትን ወታደሮቻቸውን ይዘው ወደ ጐጃም ተመለሱ።

እንግዲህ ! ጠላት ሙሉ ዝግጅት አድርጐ በመጣበት በሰሜንና በደቡብ ግንባር የመከላከያ ውጊያ ሲያደርግ ለስድስት ወራት የቆየው የኢትዮጵያ ሠራዊት፣ በአውሮፕላን በሰፊው የሚረጭበትን በዓለም ሕግ የተከለከለውን መርዝና የጋዝ ጢስ ለመቋቋም ስለአቃተው፣ ቦታውን እየለቀቀ ወደ ኋላ ከመመለስ በስተቀር ሌላ ምርጫ ሊኖረው አልቻለም። በዚህም ምክንያት፣

ኢትዮጵያ ለአንድ ቀንም ቢሆን፣ ያላትን ኃይል በሙሉ ሰብስባ ጠላትን በማግጠም የመጨረሻ ዕድሏን ሳትሞክር በሯን መልቀቅ የለባትም በማለት፣ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው የጦሩ መሪ በመሆን፣ በሰሜን ግንባር እየገፋ የመጣውን የፋሽስት ጦር፣ በማይጨው ተራራ ላይ ተጋፍጦ ለመዋጋት ውሳኔ አደረጉ።

ይህንንም ሐሳብ በተግባር ለማዋል በተምቤን በኩል የዘመቱትና ከሞት የተረፉት አዝማቾች ከያሉበት ተነሥተው "ኮረም" ላይ እንዲሰበሰቡ በተላለፈላቸው ትዕዛዝ መሠረት፣ እንደ ኢት/አቆ መጋቢት 10 ቀን 1928 ዓ.ም ከሌሊቱ በ8 ሰዓት፣ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉና ልዑል ራስ ሥዩም መንገሻ ከነረዳቶቻቸው ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ተገናኙ። በዚህም ጊዜ ከእነሱ ጋር በጦር ሜዳ ከዋሉት ታላላቅ ሰዎች መካከል፣ ደጃዝማች መሸሻ ወልዴ የከምባታ ገዥና ደጃዝማች በየነ አባ ሰብስብ፣ የኩንታ ገዥ በጀግንነት ሲዋጉ ሕይወታቸው ማለፉ ተነገረ።

ንጉሠ ነገሥቱ እነ ራስ ካሣን ይዘው፣ ኮረም ላይ ለመሰብሰብ ከቻሉ በኋላ፣ በማይጨው የጠላትን ጦር ለመውጋት የሚያስፈልገው ፕላን እንደሚከተለው ተዘጋጀ።*

| | | |
|---|---|---|
| 1. <u>የጦሩ ጠቅላይ አዛዥ፣</u> | | ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ንጉሠ ነገሥት |
| 2. <u>የመኻል ግንባር አበጋዝ፣</u> | | ራስ ካሣ ኃይሉ |
| በውስጣቸው፣ | — | ራስ ከበደ መንገሻ |
| | — | ፊታውራሪ አሸናፊ |
| | — | ሊጋባ ጣሰው ዋለሉ |
| | — | ፊታውራሪ አርአያ |
| | — | ነጋድራስ ወዳጆ አሊ |
| | — | ደጃዝማች አበራ ተድላ |
| 3. <u>የቀኝ አበጋዝ፣</u> | — | ራስ ሥዩም መንገሻ |
| በውስጣቸው፣ | — | የወለጋ ጦር |
| | — | የፈረስ ዘበኞች |
| | — | ስናድር ያኸ |
| | — | ቀኛዝማች ወልደዮሐንስ (የመድፈኞች ክፍል) |
| | — | ፊታውራሪ ተፈሪ ተድላ |
| | — | ሊቀመኳስ ኃይለማርያም |
| 4. <u>የግራ አበጋዝ፣</u> | — | ራስ ጌታቸው አባተ |
| በውስጣቸው፣ | — | የከምባታ ጦር |
| | — | የገንዘብ ሚኒስቴር ጦር |

* ቀ.ኃ.ሥ ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ ገጽ 195-97



ንጉሠ ነገሥቱ በማይጨው ግንባር ላይ ሆነው
(ፎቶ ኢ.ጥ.ም.ተ)

- የፖስታ ሚኒስቴር ጦር
- የማለፊያ ጠመንጃ ያዥ ጦር
- የባልደራስ ጦር

5. ከጦሩ ጠቅላይ አዛዥ፣ ከንጉሠ ነገሥቱ አጠገብ፣
- ፊታውራሪ ብሩ ወልደገብርኤል (የቀድሞ የጦር ሚኒስትር)
- ደጃዝማች ወንዲራድ ድፋባቸው
- ደጃዝማች ወንድወሰን ካሣ
- ደጃዝማች አበራ ካሣ
- አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ (ኋላ ጸሐፊ ትዕዛዝ)
- ዶክተር መላኩ በያን (የጃንሆይ ሐኪም)

6. ከንጉሠ ነገሥቱ በስተግንባር፣

የክብር ዘበኛ ዋና አዛዥ፣ ቀኛዝማች መኩሪያ ባንትይርጉ፣
የክበር ዘበኛ ም/አዛዥ ፣ ግራዝማች ክፍሌ እርገቱ

7. ከንጉሠ ነገሥቱ በስተቀኝ፣
- ቀኛዝማች በልሁ ደገፉ (የእልፍኝ አስከልካይ ጦር)

8. ከንጉሠ ነገሥቱ በስተግራ፣
- ግራዝማች አበራ ግዛው (ከክብር ዘበኛ ጦር)

9. ከንጉሠ ነገሥቱ በስተጀርባ ደጀን
- ደጃዝማች አደፍርሰው ይናዱ (የእልፍኝ ዘበኞች ጦር ዋና አዛዥ)

10. ከመንፈሳዊ አባቶች፣
- ብፁዕ አቡነ ጴጥሮስ (የወሎ ጳጳስ)
- ብፁዕ እጨጌ ገብረ ጊዮርጊስ ዘመንበረ ተክለሃይማኖት (ኋላ ፓትርያርክ ዘ. ኢትዮጵያ)
- ሊቄ ገብረክርስቶስ
- ሊቀ ሊቃውንት ገብረአብ

ለማይጨው ጦርነት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ራሳቸው የሚመሩት ጦር ዝርዝሩ ከዚህ በላይ በተገለጸው ዓይነት ከተሰናዳ በኋላ፣ ውጊያው ሰኞ መጋቢት 21 ቀን 1928 ዓ.ም በኢትዮጵያ ሠራዊት እንዲጀመር ጠቅላይ የጦር አዛዡ ወስነው ነበር። የጠላት ጦር አዛዥ ማርሻል ባዶግሊዮ ግን፣ የደረሰው መረጃ ንጉሠ ነገሥቱ ጦርነቱን የሚከፍቱት አፄ ምኒልክ አድዋ ላይ እንዳደረጉት

የቅዱስ ጊዮርጊስን በዓል ጠብቀው ሮብ መጋቢት 23 ቀን ነው የሚል ስለሆነ፣ የምድር ጦሩም ሆነ የአየር ኃይሉ የውጊያ ዝግጅታቸውን አጠናቅቀው እንዲጠብቁ ጥብቅ ትዕዛዝ የሰጠው ለዚህ ዕለት ነበር። ይሁን እንጂ፣ ከኢትዮጵያ በኩል ከያለበት ተሰብስቦ፣ ከማይጨው አጠገብ "መሐን" በተባለው ቦታ እንዲገኝ የተጠራው ሠራዊት፣ በአንዳንድ እክል ምክንያት ተሟልቶ በተቀጠረው ሰዓት ባለመድረሱ፣ ጦርነቱን በፊት እንደታሰበው ሰኞ መጋቢት 21 ቀን ለመጀመር ሳይቻል ቀርቶ፣ በማግሥቱ እንዲሆን ተወሰነ።

መጋቢት 22 ቀን 1928 ዓ.ም ማክሰኞ፣ "መሐን" ከተባለው ቦታ የተሰበሰበው የንጉሠ ነገሥቱ ጦር ወደ ማይጨው እየተጓዘ ከሌሊቱ አሥር ሰዓት ላይ ከጦርነቱ ሥፍራ ሲቃረብ፣ ከአዝማቾች አለቃው ትዕዛዝ ሳይደርሰው ከኢትዮጵያ ሠራዊት በኩል አንዱ ጥድፍተኛ በተንኮል ይሁን ወይም በስሕተት የተኩስ ድምፅ በማሰማቱ፣ ጠላትም ነቅቶ የመድፍ አጸፋውን መመለስ ጀመረ። በዚህ ጊዜ፣ ምንም እንኳ የኢትዮጵያ ሠራዊት ጠላት የሰፈረበትን ተራራ በሚገባ ሳይከብና ትክክለኛውን ቦታ ሳይዝ ተኩስ መጀመሩ የሚያሳዝን ቢሆንም፣ ወደ ኋላ ለመመለስ ስለማይቻል፣ ንጉሠ ነገሥቱ ጦርነቱ እንዲቀጥል አዘዙ። ጦርነቱ ይጀመራል ተብሎ ከተጠበቀበት ከአንድ ቀን በፊት፣ የኢትዮጵያ ሠራዊት ተኩሱን እያቀጣጠለ ወደ ማይጨው ተራራ ሲገሠግስ፣ በጠላት ጦር ላይ ከፍ ያለ ድንጋጤ እንደፈጠረ ይታይ ነበር። ይሁን እንጂ፣ ማርሻል ባዶግሊዮ ገና ከመነሻው የአድዋ ታሪክ እንዳይደገምበት ካለው ሦስት የተሟላ ዲቪዚዮን የምድር ጦር ይልቅ፣ በአየር ኃይሉ በመተማመን ከፍ ያለ ዝግጅት አድርጐ ስለነበረ፣ መርዝ የሚረጩትና ቦንብ የሚጥሉት በአንድ ጊዜ ቁጥራቸው ከአንድ መቶ ሃምሳ በላይ የሆኑ አውሮፕላኖች፣ በአሥር መንታ እያንዣበቡ በኢትዮጵያ ሠራዊት ላይ እሳቱን እንደ ዝናብ እንዲያወርዱበት አስደረገ። ኢትዮጵያውያኖቹም በአንድ በኩል ከሰማይ የሚወርድባቸውን መርዝና ቦንብ፣ በሌላ በኩል ደግሞ ከምድር የሚተኰስባቸውን መድፍና መትረየስ በድፍረት እየተጋፈጡ፣ በዚያ በያዙት በጥንታዊው የሰናድር ጠመንጃና ወጨፎ ውጊያቸውን ቀጠሉ። በዚህ አኳኋን፣ ጦርነቱ በተጀመረ አምስት ሰዓቶች ባልፈጀ ጊዜ ውስጥ፣ በማይጨው ላይ ጠላት የሰፈረባቸውን አምስት ምሽጐች በጀግንነት ለማስለቀቅና የጠላትን ወታደሮች ብዙዎቹን ገድለው ብዙዎቹንም ለማባረር ችለው ነበር። ይሁን እንጂ፣ የኢትዮጵያ ተዋጊ ኃይል እየቀናው መሄዱ ንጉሠ ነገሥቱን ቢያስደስታቸውም፣ በጠላት በኩል በተለይ በአየር ኃይል የተጣለው መርዝና ቦንብ ብርቱ ጉዳት ያደረሰ በመሆኑ፣ ከሞት የተረፈው ጀግናው የኢትዮጵያ ሠራዊት ጥቂት እንዲያርፍና የሞተውም ሬሳው እየተነሣ እንዲቀበር፣ መጋቢት 23 ቀን ሮብ "መሐን" ላይ የአንድ ቀን ውሎ ይደረግ ሲሉ፣ የጦሩ ዋና አዛዥ ለየአዝማቹ ትዕዛዝ አስተላለፉ።

ከዚህ ቀደም እንደተገለጸው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከየአዝማቹ የጦር አለቃ ጋር የሚለዋወጡትን ሐሳብና የሚሰጡትን መምሪያ የጠላት ድርጅት የመገናኛ ራዲዮኑን እየጠለፈ ስለሚያቀርብለት፣ የማርሻል ባዶሊዮ አስተያየት፣ የኢትዮጵያ ሠራዊት "መሐን" ላይ ለአንድ ቀን ውሎ እንዲያደርግ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ትዕዛዝ የሰጡት፣ ያለጥርጥር ከበስተጀርባቸው ከፍተኛ ደጀን የሆነ የጦር ኃይል እስኪደርስላቸው ነው የሚል ስለሆነ፣ በጠላት ጦር ሠፈር ያደረው ሥጋት ቀላል እንዳልነበረ ታውቋል።

ለዳግማዊ ምኒልክ አድዋ ላይ ድልን ያስገኘው የየካቲቱ ጊዮርጊስ፣ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ደግሞ የመጋቢቱ ፈረሰኛው ጊዮርጊስ የጉልበት ማጠናከሪያ ዕድል የሚሰጥ እንዲሆን ተስፋ በማድረግ፣ በማግሥቱ ሐሙስ መጋቢት 24 ቀን ከጠላት ጋር ጦርነቱን እገጥማለሁ ብለው ንጉሠ ነገሥቱ ወስነው ነበር። ነገር ግን፣ በአራት ግንባር የተመደቡት ዋና ዋናዎቹ የጦር አዝማቾችና ከሞት የተረፉት የጦር አለቆች በሙሉ ተሰብስበው ይህን ንጉሠ ነገሥቱ ያቀዱትን ውጊያ ለመፈጸም የሚቻል አለመሆኑን አስረዱ። በተለይም ልዑል ራስ ካሣና ልዑል ራስ ሥዩም በገለጹት አስተያየት፣ « ... ሠራዊቱ መድከም ብቻ ሳይሆን አልቋል ማለት ይቻላል። ቢቆጠር ሕይወቱ ከተረፈው ይልቅ በመርዝ የተቃጠለውና በመድፍ ተመትቶ የሞተው ይበልጣል። በዚህ ሁኔታ ዛሬ ጦርነቱን እንደገና እንቀጥል ማለት የተረፈውን ሠራዊት አስጨርሰን እኛም አልቀን አገራችንን ማስረከብ ይሆናል። እግዚአብሔር ፈቃዱ ባይሆን ነው እንጂ፣ በትናንቱ ዕለት ጠላትን ደህና አድርገን አድቅቀነው ነበር። ጠላታችን እኛን የበለጠን በምድሩ ውጊያ ሳይሆን፣ በማናውቀውና መሣሪያው በሌለን በሰማዩ ጦርነት ነው። አሁንም ዛሬ ተነሥተን እንግጠመው ብንል፣ የሚያጠቃን ያው በተለመደው የፊሪ በትሩ ከሰማይ በሚያዘንብብን እሳትና መርዝ ነው እንጂ፣ እንደ ወንዶቹ ፊት ለፊት ቢመጣብን አንበገርም ነበር። ስለዚህ፣ የሚሻለው ወደ ኋላ ተመልሰን ከሞት የተረፈው ሠራዊታችን የሚያገግምበት ዕድል እንዲያገኝ ማድረግና፣ ሌላም ተጨማሪ ጦር ለማዘጋጀት የሚቻልበትን መንገድ ማጥናት ይሻላል ... » አሉ።

ንጉሠ ነገሥቱ ይህን ሐሳብ መቀበል አልፈለጉም። « ... እኛ ከዚህ ካለንበት ቦታ ለቅቀን ወደ ኋላ ብናፈገፍግ፣ ድሉን ለጠላታችን አረጋገጥንለት ማለት ነው። እኔ እዚህ ጦር ሜዳ የመጣሁት ለኢትዮጵያ ነፃነት ደሜን ለማፍሰስ ቆርጬ ነው። ስለዚህ፣ ከዚህ በፊት ዓለሜን ከሕዝቤ ጋር እንደተካፈልኩት፣ መከራውንም ከሕዝቤ ሳልለይ እካፈላለሁ እንጂ፣ አገሬን ለጠላት አስረክቤ ወደ ኋላ በመመለስ ሕይወቴን ለማዳን አልሞክርም። ቀድሞውንም እኔ እዚህ የመጣሁት፣ ድል አደርጋለሁ ብዬ አይደለም። ድል ብሆንም፣ ሕይወቴ እስኪያልፍ ድረስ ተዋግቼ ተግባሬን ፈጽሜ ሞትን ለመቀበል ነው። ሁላችሁም እንደምታውቁት አሁን ያለነው በሁለት ዓይነት ሞት መካከል ነው። አንደኛው ሞት፣ ከጠላት ጋር ተዋግቶ መሞት ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ ሲሸሹ በጠላት እጅ ወድቆ መሞት ነው። ከእነዚህ ከሁለቱ ይመረጥ ቢባል፣ያለጥርጥር በጀግንነት ሲዋጉ መሞት ከሁሉም የበለጠ ክብር ነው። እኔ ዓላማዬ ይኸ ስለሆነ፣ የፈቀደ ከእኔ ጋር ይሙት። እኔ ግን ወደ ኋላ አልመለስም ... » አሉ።

መኳንንቱና ሹማምንቱ ይህን የጃንሆይን ውሳኔ ካዳመጡ በኋላ፣ ምን እንደሚሻል እርስ በርሳቸው መመካከር ጀመሩ። በመጨረሻው ሁሉም በአንድነት ሆነው በመሐላ ቃል የተስማሙበትን ሐሳብ፣ ብፁዕ አቡነ ጴጥሮስ እና ብፁዕ እጨጌ ገብረጊዮርጊስ ባሉበት ለንጉሠ ነገሥቱ አቀረቡ።

« ... ወደ ኋላ ተመልሰን ለጦርነት እንዘጋጅ ስንል፣ ተስፋ ቆርጠን ቦታችንን እንልቀቅ ማለት አይደለም። አሁን በሕይወት የተረፍነው ብቻችንን ሆነን ጠላታችንን ገጥመን ብንሞት፣ ጥቅም የሰጠ ሞት ነው ማለት አይቻልም። ነገር ግን፣ ወደ ኋላ ተመልሰን ቦታ እየያዝን ብንዘጋጅና ከአንዱ ሥፍራ ወደ ሌላው እየተዘዋወርን ብንዋጋ፣ ጠላታችንን ማስጨነቅና ማዳከም እንችላለን።

እንደዚህ ካደረግን፤ ዛሬ ለጠላታችን የቀናው ዕድል፤ ነገ ለእኛ የማይሆንበት ምክንያት የለም። ስለዚህ፤ በሌለን አቅም ጦርነቱን ተጋፍጠን መሞት፤ ለጠላት ምቹ የሆነ ዕድል መስጠት ይሆናል ብለን ስለሠጋን፤ ወደኋላ ተመልሰን እንዘጋጅ አልን እንጂ፤ ለሕይወታችን ሳስተን ወይም ፍርሃት አድሮብን አለመሆኑን ሁላችንም አንድ ሆነን በመሐላ የምናቀርበውን ሐሳብ ጃንሆይ ይወቁልን … ›› 

ንጉሠ ነገሥቱ ይህንን ከተከታዮቻቸው መኳንንትና ሹማምንት የቀረበላቸውን ሐሳብ ካዳመጡ በኋላ፤ አሁን መዋጋቱ ይቅርና ወደ ኋላ እንመለስ የተባለውን ሐሳብ ለመቀበል እጅግ ሲቸገሩ ታየባቸው። በዚህ ጊዜ ከመንፈሳዊ አባቶች አንዱ የሆኑት ሊቀ ሊቃውንት ገብረአብ፤ አንድ ጠንከር ያለ ንግግር አደረጉ። ‹‹ … ግርማዊ ጃንሆይ ! መቸም ለኢትዮጵያ ኃላፊነትን የተቀበሉት ከእግዚአብሔር ስለሆነ፤ የእነ ዳዊትን፤ የነናቡከ ደነፆርን፤ የነምናሴን፤ የነ አፄ ልብነ ድንግልን ታሪክ እያሰቡ፤ ወደኋላ ተመልሰው እግዚአብሔር እስኪፈቅድልዎ ድረስ መከላከል ይሻልዎታል። አሁን የገጠመዎትን ንዴት ተከትለው ቢሞቱ፤ ዋጋ የሌለው ሞት ይሆናል። ደግሞም ምንም ሞትን ቢመኙት በድንገት በጠላት መማረክም መኖሩን ማሰብ አለብዎት … ›› አሉ። በዚህ ሊቀ ሊቃውንት ገብረአብ በወረወሩት የማስረጃ ቃል፤ ጃንሆይ እጅግ ተበሳጭተው ሰውነታቸው ሲለዋወጥ ታየ። እጃቸውን ከታጠቁት ሽጉጥ ላይ አስደግፈው መሣሪያቸውን እየነቀነቁ፤ ‹‹ … እኔን በጣልያን እጅ ተይዞ ይማረካል ብለው አይጠርጥሩ … ›› በማለት ዓይናቸውን ትክ አድርገው ተመለከቷቸው። በዚያች ሰዓት ይህ የጃንሆይ አነጋገርና ሁኔታ በዙሪያቸው በተሰበሰበው መኳንንትና ሹማምንት ላይ ከፍ ያለ ድንጋጤ አስከትሎ ነበር። ወዲያውም፤ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ ብድግ ብለው የሚከተለውን ቃል ተናገሩ።

‹‹ … ጃንሆይ ! ሞትን እኮ መቸውንም አያጡትም። ትልቁ ጥያቄ ምን ዓይነት ሞት ይሻላል ? ነው። በደህና አኳኋን ባልተዘጋጀ ጦር ተዋግተው በአጭሩ ቢሞቱ፤ አገርዎን መበደል ይሆናል። ነገር ግን፤ የተቻለዎትን ያህል ተዘጋጅተው ረዘም ላለ ጊዜ ቢዋጉና ቢሞቱ፤ ለአገርዎ መልካም ስም ይሆናል። ከእኔ በፊት መኳንንቶችና የጦር አለቆች ደህና አድርገው ተናግረውታል። ለጊዜው ወደኋላ ተመልሰን ብንዘጋጅና እግዚአብሔር እስኪፈቀድ ድረስ በየአውራጃው እየተዘዋወርን ለአገራችን ሥቃዩን ብንቀበልላት የተገባ ይሆናል። መቸም፤ ወደ ኋላ ተመልሶ መዘጋጀት ይሻላል ሲባል፤ ለጠላት ዕድል መስጠት ነው ተብሎ መታሰብ የለበትም። የዝግጅት ጠቀሜታው ጠላትን ለመከላከል ብቻ ሳይሆን፤ ከዚያም አልፎ ድል ለማድረግ መሆኑን አብሮ ማሰብ ያስፈልጋል። አሁን ጃንሆይ ነገሩን በጥሞና ቢመለከቱት፤ እዚህ በዙሪያዎ ከተሰበሰብነው መኳንንትና ሹማምንት፤ በዚያውም ላይ ዘበኛውና አሽከሩም ተጨምሮ ሁሉም ሐሳቡን የገለጸው፤ ወደኋላ ተመልሰን እንዘጋጅ የሚል ነው እንጂ፤ እዚሁ አለንበት ተዋግተን እንሙት ብሎ የቆረጠ ደፋር አልታየም። ስለዚህ፤ እስከሚቻለን ድረስ ለአገራችን ነፃነት ለመታገል፤ በሚያመች መንገድ ሁሉ ከአደጋ ለመዳን መሞከር የተገባ ስለሆነ፤ እዚህ እንደ ተሰበሰብን የሰማይ አምራውን አጥለቅልቆ በእናታችን ላይ ጠላታችን በሚነዛብን መርዝ፤ ሁላችንም ከምንጠፋ ይህን ቦታ ብንለቅ ይሻላል … ›› አሉ።

ከዚህ በላይ እንደሚታየው፤ ራስ ካሣ ባደረጉት ንግግር እንደ ገለጹት፤ በንጉሠ ነገሥቱ ዙሪያ ተሰብስበው አስተያየት ሰጭዎች የሆኑት ከመሳፍንቱና ከመኳንንቱ ሌላ፤ የግቢ ዘበኞችና አጋፋሪዎች፤ የእልፍኝ አሽከሮችና ዕቃ ቤቶች

ጭምር ናቸው። በዚህ ጉዳይ ከራስ ካሣ አነጋገር መረዳት የሚቻለው፤ ይህን በመሰለ ስለ አገር ጉዳይ በሚደረግ ታላቅ ውይይት ላይ፤ ከመኳንንቱና ከጦር መሪዎቹ ውጭ ሌሎቹ ለምን አስፈለጉ ? ሳይሆን አይቀርም። በጃንሆይ በኩል ደግሞ የተወሰደው እርምጃ የታላላቆቹን ብቻ ሳይሆን የትንንሾቹንም ሐሳብ ማዳመጡ አይከፋም በሚል መንፈስ ይመስላል። ያም ሆነ ይህ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ለራስ ካሣ በሰጡት መልስ፤ ምንም እንኳ ብዙ ጊዜ እንደሚያደርጉት "አንተ እንዳልከው" የሚል ቃል ባይጨምሩበትም፤ ሐሳባቸውን ለውጠው ጦሩ ከማይጨው እንዲመለስ የወሰኑት፤ የታወቁት መስፍን ካቀረቡላቸው ሰፊ አስተያየት በኋላ መሆኑ ይታያል። « ... አሁን ሁላችሁም ጦሩ ወደ ኋላ ተመልሶ ሌላ ዝግጅት ቢደረግ ይሻላል ብላችሁ የተናገራችሁት፤ እኔን ለመደለል ሳይሆን ቁርጥ ሐሳባችሁ መሆኑን በመንፈስ አባቶቻችን ፊት በመሐላ አረጋግጣችሁልኛል። እንግዲህ፤ የሁላችሁም ሐሳብ እንደዚህ አንድ ከሆነ፤ እኔም ያቀረባችሁት እንዲፈጸም ይሁን እላለሁ ... »

በዚህ አኳኋን፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከማይጨው ወደ ኋላ መመለስን ሲፈቅዱ፤ በስብሰባው ላይ ስምምነት የተደረገው፤ ጦሩን ይዘው ወደ ኮረም ለመጓዝና በዚያም አንዳንድ ዝግጅት እያደረጉ ጠላትን ለመውጋት ነበር። ነገር ግን፤ ይህ ዕቅድ ጥሩ ነው ብሎ ማይጨው ላይ የፎከረው ሠራዊት፤ ከግማሹ ይበልጥ የጉዞውን አቅጣጫ እየለወጠ ወደ ልዩ ልዩ ሥፍራ መሸሽን መረጠ። እንደ ኢት/አቆ መጋቢት 26 ቀን 1928 ዓ.ም ቅዳሜ ጠዋት ንጉሠ ነገሥቱ አሸንጌ ሲደርሱ፤ አብዛኛው የኢትዮጵያ ተዋጊ መበታተኑንና የጠላት ኃይልም የደረሰውን መረጃ በመጠቀም ከእሳቸው ቀድሞ ኮረምን መያዙን ሰሙ። ከዚህም በላይ የጠላት አውሮፕላኖች በተከተላቸው ሠራዊት ላይ ቦንብ እየጣሉ ብዙ ጉዳት አደረሱባቸው።

እንግዲህ ፤ ጦሩ ግማሹ ተበፋ ቀርጦ ሲበታተንና ወደ ክዳት ሲያዘነብል፤ ታማኝ የሆነውንም በአውሮፕላን የሚጣልበት ቦንብና መርዝ ሲጨርሰው፤ በምን አቅምና በምን መንገድ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ውጊያውን መቀጠል ይችላሉ ? ... ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ያሉትም ትልልቆቹ የጦር አለቆች፤ ጠላት የአየር ኃይሉን እያስፋፋ በመጣበት ሁኔታ ለመመከት ጨርሶ እንደማይቻል በግልጽ ስለተረዱት፤ ወደ አዲስ አበባ ተመልሶ በመመካከር አንድ ነገር ከመወሰን በስተቀር ሌላ ምርጫ አለመኖሩን አመኑበት። በዚህ ሐሳብ ንጉሠ ነገሥቱም ተስማምተው፤ ጉዞው ወደ አዲስ አበባ እንዲያመራ ተወሰነ። በዚህ መሠረት፤ እንደ ኢት/ አቆ መጋቢት 27 ቀን 1928 ዓ.ም፤ ከአሸንጌ ተነሥተው አንድ ሳምንት ያህል ተጉዘው፤ ሚያዝያ አምስት ቀን ሌሊቱን ላሊበላ ገዳም ደረሱ። በዚያም በራስ ካሣ ቤት አድረው በማግሥቱም ውሎ ከአደረጉ በኋላ፤ ሚያዝያ ሰባት ቀን ጠዋት ተነሥተው፤ ለአሥራ አምስት ቀናት እጅግ አስቸጋሪ የሆነውን መንገድ በበቅሎና በእግር እየተጓዙ፤ በደላንታና በወረሂመኑ፤ በለገሂዳና በጃማ፤ በመርሐ ቤቴና በሰላሌ በኩል አልፈው፤ ከፍቼ ከተማ ሲደርሱ፤ አውቶሞቢል ተልኮላቸው፤ ሚያዝያ 22 ቀን 1928 ዓ.ም ከጠዋቱ በሦስት ሰዓት አዲስ አበባ ገቡ።*

* ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ ንብረወልድ እንግዳወርቅ የማይጨው ታሪክ

# ምዕራፍ ፲፩

## የፋሽስት ጦር ወደ አዲስ አበባ ተቃረበ

### ምን ማድረግ ይሻላል?

ማንም ሰው እንደሚያውቀው፣ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ የገፎኔቡን የመንግሥታት ማህበር ሕግ በመተማመን፣ ኢትዮጵያን ለጦርነት ሳያዘጋጇት እስከ መጨረሻው ሰዓት ድረስ በመቆየታቸው፣ ለፋሽስት ድል አድራጊነት ዕድል ሰጥተዋል የሚል ወቀሳ ተሰንዝሮባቸዋል። ይህም ወቀሳ የተመሠረተው፣ ኢትዮጵያ ባላት አቅም ቀደም ብላ አንዳንድ የመከላከያ ዝግጅት አድርጋ ቢሆን ኖሮ፣ ምንም እንኳ እንደ አባ ዳኘው ምኒልክ የአድዋን ዓይነት ድል ባያጋጥማትም፣ የፋሽስትን ጦር ረዘም ላለ ጊዜ መመከት ትችል ነበር በሚል መንፈስ ነው። ይህ አስተያየት እንደተጠበቀ ሆኖ፣ በዚያን ዘመን ንጉሠ ነገሥቱ ያጋጠማቸውን ችግርና የነበራቸውንም አመለካከት ለመገንዘብ መሞከር እንደሚያስፈልግ፣ የብዙ ሰዎች እምነት እንደሆነ ታውቋል።

1. እንደ ምኒልክ ባለሙሉ ሥልጣን ሆነው፣ ዘውድ ከጫኑበት ከአምስቱ ዓመታት ጀምሮ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና ዓላማቸው አድርገው የያዙት ኢትዮጵያን ወደ ሥልጣኔ ለማሻገር፣ አስፈላጊውን ጥረት ማድረግ እንጂ፣ ለነፃነት መከላከያ ጦር ማዘጋጀት አልነበረም። የውጭ ጠላት ሊመጣ ይችላል በማለት የጦር መሣሪያዎች ከውጭ አገር እየገዙ ጦሩን ለማደራጀት ቢፈልጉም፣ ኢትዮጵያን አጥረው በዙሪያዋ የሠፈሩት ኮሎኒያሊስቶች፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሣይና ጣልያን እንደማይፈቅዱላቸውና መንገዱንም እንደሚዘጉባቸው ማየት ያስፈልጋል። ለምሳሌም ያህል፣ ለታሪክ እጅግ አሳዛኝ ሆኖ የሚቀርበው፣ ገና ከጦርነቱ በፊት፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ለአገር ውስጥ ፀጥታ መጠበቂያ እንዲሆን በእንግሊዝ፣ በፈረንሣይና በጣሊያን መንግሥታት ቁጥጥርና ፈቃድ ተገዝተው የነበሩት ቀላል መሣሪያዎች፣ ከጂቡቲ ወደ አዲስ አበባ በባቡር እንዳይሣፈሩ የፈረንሣይ ባለሥልጣኖች አግደው መያዛቸው ነው። በፈረንሣዮች በኩል ይህ አሳዛኝ እርምጃ የተወሰደው፣ በዚያን ዘመን የነበረው የፒየር ላቫል መንግሥት፣ የሙሶሊኒ ዋና ደጋፊ በመሆኑ ነበር። ንጉሠ ነገሥቱ እስከ መጨረሻው ሰዓት ድረስ በተስፋ እንደጠበቁት፣ እነዚህ መሣሪያዎች ከተያዙበት ከጂቡቲ ተለቅቀውላቸው ቢሆን ኖሮ፣ በተለይ በማይጨው በተደረገው ግጥሚያ ጀግናው የኢትዮጵያ ሠራዊት በጠላት ላይ ከፍ ያለ ጉዳት ለማድረስ እንደሚችል የሚጠረጠር አልነበረም። ነገር ግን፣ የፈረንሣይ ባለሥልጣኖች ኢትዮጵያ ይህ ዕድል እንዲገጥማት አልፈለጉም። የማይጨው ጦርነት ከተበተነና የፋሽስት ጦር ድል እየቀናው ወደ አዲስ አበባ ማምራት ከጀመረ በኋላ፣ ፈረንሣዊው የጂቡቲ አገረ ገዥ፣ የተያዙት መሣሪያዎች ወደ ኢትዮጵያ እንዲተላለፉ ፈቃዱ ከፓሪስ ደርሶኛል በማለት፣ በባቡር አሳፍሮ ወደ አዲስ አበባ ሲልካቸው፣ የፋሽስት ጦር ድሬዳዋ ላይ ጠብቆ ተረከበው።

2. ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል ሆና ከነፃዎቹ መንግሥታት ጋር የተከበረ ወንበር ስለያዘች፣ የሙሶሊኒ መንግሥት የማህበሩን ደንብ ጥሶ ነፃነቷን ለመግፈፍና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ በጦር ኃይል ይወጋታል ብለው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አልጠበቁም። ወቃሾቻቸው የሚሉት "መጠበቅ ነበረባቸው" ነው። እንደተባለው፣ ኢትዮጵያ ጠላት ሊነሣባት ይችላል ብለው ቢጠብቁስ፣ ቀደም ሲል እንደ ተብራራው፣ በጦር መሣሪያዎች በኩል ምን ያህል ዝግጅት ለማድረግ ይቻላቸው ነበር ? ተብሎ ለሚቀርበው ጥያቄ መልሱን መስጠት ያስፈልጋል። ከአድዋ ጦርነት በኋላ በ1906 ዓ.ም ኢትዮጵያን የሚያዋስኗት የሦስቱ ኮሎኒያሊስት መንግሥታት እንግሊዝ፣ ፈረንሣይና ጣልያን ባደረጉት ስምምነት፣ ያለ እነሱ ፈቃድ የንጉሡ ነገሥቱ መንግሥት የጦር መሣሪያዎች እየገዛ ወደ አገሩ ማስገባት አይችልም ብለው ወስነዋል። ስለዚህ፣ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ለጦርነት ተዘጋጅተው መጠበቅ ነበረባቸው እየተባለ የሚሰጠው ትችት፣ የሕዝብ ሠራዊት ቁጥር በመጨመር ካልሆነ በስተቀር፣ በጦር መሣሪያዎች ረገድ እንኳንስ በአየር ኃይል፣ በታንክና በመድፍ ቀርቶ፣ እንደ መትረየስ የመሳሰሉትንም ቀላል መሣሪያዎች ለመግዛት የማይችሉ መሆናቸው መታወቅ አለበት።

3. ከጥንት ጀምሮ የኢትዮጵያ ወዳጆች ናቸው የሚባሉትም የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት፣ ግፈኛው ፋሽስት ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ያንን ያህል ዝግጅት አድርጐ ሲመጣ፣ አንዳች እርምጃ ሳይወስዱ፣ ወይም ደግሞ ለኢትዮጵያ ነፃነት መከላከያ እርዳታ ሳይሰጡ፣ የቃላት ድጋፍ በመለገስ ብቻ ያበቃሉ ብለው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አልጠበቁም።

4. የኢትዮጵያን ነፃነት ለመግፈፍ ተዘጋጅቶ ጦርነቱን የከፈተው የፋሽስት መንግሥት፣ እንኳንስ ለራሱ፣ ለሌሎቹም አገሮች የሚተርፍ የጦር መሣሪያ ፋብሪካዎች ያሉት መሆኑን በግልጽ እያዩ፣ ዮናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካና አንዳንድ የአውሮፓ አገሮች፣ ለጣልያንና ለኢትዮጵያ የጦር መሣሪያዎች አንሸጥም የሚል መግለጫ በማውጣት፣ ይህችን ደሃ አገር እስከዚህ ድረስ ይበድሏታል ብለው፣ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ አላሰቡም።

5. ሊግ ኦፍ ኔሽን በጣሊያን ላይ የወሰነውን የኤኮኖሚ እገዳ ቅጣት፣ በትክክል እንፈጽማለን ብለው ቃል የገቡት አብዛኛዎቹ የመንግሥታት ማህበር አባሎች፣ ውስጥ ውስጡን ከሙሶሊኒ ጋር ያላቸውን ወዳጅነት በማጥበቅ፣ ለፋሽስት እንዱስትሪዎች ማምረቻ አስፈላጊ የሆኑትን ጥሬ ዕቃዎች በመሸጥና በለውጡም የፋብሪካዎቹን ውጤቶች እየገዙ ግፈኛውን መንግሥት ለመጥቀም እስከዚህ ድረስ እርምጃ ይወስዳሉ ብለው ቀዳማዊ ኃይለሥለሴ አልጠረጠሩም።

6. በብዙ መቶ የሚቆጠሩ የአየር ኃይል አውሮፕላኖችንና፣ በብዙ መቶ ሺህ የሚቆጠሩትን ወታደሮች በዘመናዊ መሣሪያዎች ያስታጠቀው የፋሽስት ጦር፣ ያለ አንዳች ዘመናዊ መሣሪያ በጀግንነቱ ብቻ የሚከላከለውን የኢትዮጵያን ሠራዊት ማሸነፍ ስለአቃተው፣ በዓለም ሕግ የተከለከለውን መርዝና የጋዝ ጢስ እየረጨ ሰላማዊውን ሕዝብ ጭምር በግፍ ሲጨርስ፣

ታላላቆቹ መንግሥታትና ሊግ ኦፍ ኔሽን በዝምታ ይመለከታሉ ብለው ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ አልገመቱም።

እንግዲህ ! ኢትዮጵያ ነፃነቷን ለመግፈፍ ከፍተኛ ዝግጅት አድርጐ ከመጣባት ጠላት ጋር ለሰባት ወራት በብርቱ ከተዋጋች በኋላ፣ ድል ሆናለች። ድል ለምን እንደሆነች ? በንጉሠ ነገሥቱ በኩል የሚታዩት ዋና ዋናዎቹ ምክንያቶች ምንና ምን መሆናቸው ከዚህ በላይ በዝርዝር የተገለጹት ናቸው። አሁን ደግሞ ከዚህ ቀጥሎ የሚወሰዱትን እርምጃዎች መመልከት ያስፈልጋል።

## በጫካ እንዋጋ ? ወይስ በዤኔቭ እንሟገት ?

እንደ ኢ/አቆ ሚያዝያ 22 ቀን 1928 ዓ.ም ንጉሠ ነገሥቱ ከዘመቻው ተመልሰው አዲስ አበባ በገቡበት ዕለት፣ ከእንግዲህ ወዲህ ለነፃነት የሚደረገው ትግል በምን መልክ መሆን እንዳለበት ተነጋግሮ ለመወሰን፣ በታላቁ ቤተመንግሥት እልፍኝ አዳራሽ ከፍተኛ ጉባኤ ተደርጐ ነበር። በዚህ ስብሰባ ላይ ተካፋይ ሆነው የተገኙት፣ በአንድ በኩል ንጉሠ ነገሥቱን ተከትለው ከዘመቻው የተመለሱት ታላላቅ መኳንንትና የጦር አለቆች፣ ሹማምንትና የቤተመንግሥት ሠራተኞች ሲሆኑ፣ በሌላ በኩል ደግሞ አዲስ አበባ ቆይተው አንዳንድ ከፍተኛ የኃላፊነት ሥራ ሲያከናውኑ የነበሩት ባለሥልጣኖች ናቸው። በዚህ ስብሰባ ላይ እንዲመከርባቸው የቀረቡት ዋና ዋናዎቹ ሐሳቦች፣

፩ኛ/ ከእንግዲህ ወዲህ ሦስት ቀናት በማይሞላ ጊዜ ውስጥ የጠላት ጦር መናገሻ ከተማውን እንደሚይዝ ስለታወቀ፣ የንጉሠ ነገሥቱ የመንግሥት መምሪያ ከአዲስ አበባ ወደ ጐሬ የሚዛወርበትን፣

፪ኛ/ በሁለት ግንባር ጦር ማዘጋጀትና የመጀመሪያው በበረህና በጣርማ በር በኩል፣ ሁለተኛው በአህያ ፈጅና በጅሁር አፋፍ በኩል ተመድበው ጠላትን ለመውጋት እንዲችሉ የሚደረግበትን፣

፫ኛ/ በሁለት ግንባር ውጊያ ለመክፈት በቂ ጦርና ሠራዊት ለማግኘት ካልተቻለ፣ ትግሉ በጫካ በሽፍትነት መልክ የሚከናወንበትን፣

፬ኛ/ የዓለም መንግሥታት ማህበር ምንም እንኳ እስከዛሬ ድረስ የቃል ድጋፍና ፍርድ ከመስጠት በስተቀር፣ የጦር ኃይል እርዳታ ነፍጐን የቆየ ቢሆንም፣ ምናልባት ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው ማህበሩ ሥራውን በሚመራበት ዤኔቭ ላይ ተገኝተው፣ ከአምሳ በላይ ለሆኑት የመንግሥታት እንደራሴዎች ቢያመለክቱ፣ ጠቃሚ ነገር ለማግኘት የሚቻልበትን ተነጋግሮ ለመወሰን ነበር።

በእነዚህ ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ አስተያየት እንዲሰጥባቸው በተጠየቀ ጊዜ፣ የስብሰባው ተካፋዮች የሆኑት ሰዎች ቁጥራቸው ከመብዛቱ የተነሣ፣ ለመደማመጥና ለፍሬ ነገሮቹ ማሠሪያ ለማግኘት ስለአስቸገረ፣ አንዳችም እርምጃ ሳይወሰድ ጉባኤው በማግሥቱ እንዲቀጥል ተወስኗል በሚል መግለጫ ተበተነ።

በዚህ ስብሰባ ላይ ከተካፈሉት አብዛኛዎቹ፣ ከእልፍኝ አዳራሹ ወጥተው ወደየቤታቸው ከሄዱ ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣ በልዑል ራስ ካሣ አማካይነት ከመሳፍንቱና ከመኳንንቱ፣ ከሚኒስትሮቹና ከጦር አለቆቹ መካከል ዋና ዋናዎቹ እየተመረጡ፣ ከምሽቱ ከሁለት ሰዓት ጀምሮ ጃንሆይ በተገኙበት ራት እየተበላ አንድ የተለየ ስብሰባ እንዲካሄድ ተደረገ። በዚህ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው በመሩት ጉባኤ ላይ ንግግር የተደረጉባቸው ጉዳዮች፣ ቀደም ሲል በተከናወነው በመጀመሪያው ስብሰባ ላይ ከቀረቡት የተለዩ አልነበሩም። ልዩነታቸው ከተካፋዮቹ ቁጥር ማነስ የተነሣ በቀለጠፈ መንገድ ውይይት መደረጉና፣ በመጨረሻውም አስፈላጊው ውሳኔ መሰጠቱ ነበር። በዚህም መሠረት፡-

፩ኛ/ ከእንግዲህ ወዲህ ጦር አሰባስቦ ጠላትን ፊት ለፊት ለመግጠም የሚያስችል መሣሪያም ሆነ በቂ ሠራዊት ስለሌለ፣ ለነፃነት የሚደረገው ትግል በጫካ የሽምቅ ውጊያ (በአርበኝነት) ከማድረግ በስተቀር ሌላ አማራጭ መንገድ አለመኖሩን ሁሉም ተስማምተውበት በሙሉ ድምፅ ተወሰነ።

፪ኛ/ ጠላት ወደ አዲስ አበባ ከተማ እየተቃረበ ስለሆነ፣ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት መምሪያ ሳይውል ሳያድር ወደ ይልባቦር ጠቅላይ ግዛት ጐሬ ከተማ እንዲዛወር ተወሰነ። በዚህም ጊዜ ጐሬ ላይ ለሚካሄደው የመንግሥት አስተዳደር ቢትወደድ ወልደጻድቅ ጐሹ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እንደራሴ ሆነው ተሾሙ።

፫ኛ/ በመጨረሻው ብዙ የሐሳብ ልውውጥ የተደረገበት ትልቁ ጉዳይ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው ዠኔቭ ሄደው የዓለም መንግሥታትን እርዳታ ቢጠይቁ፣ ይጠቅማል ወይስ አይጠቅምም በሚለው ሐሳብ ላይ ነው። በዚህ ጉዳይ ሦስት ሰዎች በየተራ የገለጿቸው አስተያየቶች የሁሉንም ሐሳብ በማስተባበር ለውሳኔ ያመቻች ሆኖ ተገኘ።

ሀ/ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣

የስላሴና የበጌምድር ገዥ፣

‹‹ ... መቾም አገራችን ላይ ትልቅ አደጋ ወድቋል። ይህም አደጋ ነፃነታችንን የሚገፍ ስለሆነ፣ እግዚአብሔር በቸርነቱ እስከሚፈቅድልን ዕድሜ ድረስ፣ ያለማቋረጥ ተጋድሎ ማድረግ አለብን። የምናደርገውም ተጋድሎ ሕይወታችንን በሚያሳጥር መንገድ ሳይሆን፣ ነፃነታችንን እስከምናስመልስ ድረስ፣ በተቻለ መጠን ራሳችንን እየጠበቅን መሆን አለበት። ማይጨው ዘመቻ ላይ ሆነን፣ ባሉን መሣሪያዎችና ባሉን ተዋጊዎች ጠላታችንን በሚገባ ማጥቃታችን አልቀረም ነበር። ጠላታችን ግን ፊት ለፊት ገጥሞ ከመዋጋት ይልቅ፣ በአውሮፕላን መርዝና እሳት በሕዝባችን ላይ መርጨትን እንደ ጀግንነት ሥራ አድርጐ ስለቆጠረው፣ ልንቋቋመው በማንችለው መንገድ ሠራዊታችንን ጨረሰብን። በዚህ ሁኔታ መቀጠሉ የበለጠ አደጋ ላይ እንደሚጥለን በማየት፣ የተረፈውን ጦራችንን ወደኋላ እንዲያፈገፍግ አድርገን ለውጊያችን ዘዴ ብንፈልግለት ይሻላል በማለት ለጃንሆይ አመለከትናቸው። ጃንሆይ "እምቢ" አሉን። እምቢ ሲሉም፣ እንዲሁም ለይስሙላ እምቢ ብለዋል ለመባል አልነበረም። በጉዳዩ አስበውበት ነው። እኔ የመጣሁት

ከጠላት ጋር ተዋግቼ ድል ለማድረግ ብቻ ሳይሆን፤ መሸነፍ መኖሩንም ሳልረሳ ነው። ስሸነፍም እስከ መጨረሻው ተዋግቼ ደሜን ለማፍሰስ ቆርጬ ስለሆነ፤ የፈለገ ከእኔ ጋር ይሙት። ነፍሱን የወደደ ደግሞ ወደ ኋላ ተመልሶ ለመዳን ይሞክር። ... ብለው እምቢታቸውን አጠንከሩብን። በዚህ ጊዜ ሁላችንንም እጅግ አሳሰቡን። ቢቸግረን፤ ሁላችንም አጥብቀን መለመኑን ቀጠልን። ጃንሆይ! ሞትን እኮ ምንጊዜም ያገኙታል። እኛ የምንለምንዎ፤ ሞትን በእግዚአብሔር እርዳታ እያዘገዩ፤ ለአገርዎ ነፃነት የሚያደርጉትን ተጋድሎ እንዲቀጥሉ ነው አልናቸው። እግዚአብሔር ይመስገን! ልመናችንን ሰምተውልን ይኸው ዛሬ ከማይጨው አልቂት ድነን፤ አዲስ አበባ ተመልሰን በጃንሆይ ዙሪያ ለመሰብሰብና፤ ለዛሬውና ለነገው የምናደርገውን ተነጋግረን ለመወሰን ዕድል አግኝተናል።

አሁን ብዙ ቁም ነገሮች ተወያይተን ከወሰንን በኋላ፤ አንድ አልባት ሳናደርግለት የቀየነው ጉዳይ፤ ጃንሆይ የዓለም ነገሥታቶች ባቋቋሙት ማህበር ቤት ተገኝተው፤ በኢትዮጵያ ላይ የደረሰውን መከራ ቢያስረዱና እርዳታ ቢጠይቁ፤ ይጠቅማል ? ወይስ አይጠቅምም ? በሚለው ሐሳብ ላይ ነው። እንደ እኔ እንደ እኔ ከሆነ፤ ጃንሆይ ሔደው ቢያመለክቱ፤ የሚበጅ ይሆናል። ዕድሉ ከቀናቸው፤ ጠላታችንን የምንወጋበት እርዳታ አግኝተው ይመጡ ይሆናል። ካልሆነ ደግሞ፤ በሚያመቸው በአንደኛው ጠረፋችን በኩል ወደ አገራቸው ተመልሰው አርበኝነታቸውን ይቀጥሉበታል ... »

ለ/ ብላቴን ጌታ ሕሩይ ወልደሥላሴ፤
የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር

ልዑል ራስ ደህና አድርገው ገልጸውታል። የአገርን ነፃነት ለሚያህል ትልቅ ጉዳይ ጥረት ማድረግ የሚያስፈልገው፤ በሁሉም አቅጣጫ ነው። በጦር ሜዳውም፤ በፖለቲካውም፤ በፕሮፓጋንዳውም የሚከናወኑ ብዙ ነገሮች አሉ። ንጉሠ ነገሥታችን በጦሩ ሜዳ በሠራዊታቸው መካከል ሆነው ተዋግተዋል። መከራውንም በቆራጥነት ተቀብለዋል። አሁን ደግሞ በፖለቲካው ሜዳ ላይ ለመታገል፤ ዤኔቭ ሔደው ለመንግሥታት ማህበር የሚያቀርቡት አቤቱታ፤ ምናልባት በእግዚአብሔር እርዳታ፤ የታላላቆቹ አገሮች ሕሊና ተቀስቅሶ ለዚች በስቃይ ላይ ለምትገኝ አገራችን ይደርሱላት ይሆናል ብለን ተስፋችንን ማጽናት አለብን። ስለዚህ፤ ልዑል ራስ እንደ ተናገሩት የግርማዊነታቸውን ወደ ዤኔቭ መሔድ ከልብ የምደግፍ መሆኔን በታላቅ ትሕትና እገልጻለሁ።

ሐ/ አቶ መኰንን ሀብተ ወልድ፤
የንግድ ሚኒስቴርንና የፖስታ ቴሌፎን ሚኒስቴርን በተጠባባቂነት የሚመሩ፤

ግርማዊ ጃንሆይ !

ከእኔ በፊት ታላላቆቼ ተናግረውታል። እኔም ሐሳቤን እንድገልጽ ግርማዊነትዎ ያዘዙኝን ለመፈጸም እንጂ፤ የተለየ አዲስ ነገር የማቀርበው ይኖራል ብዬ አይደለም። ሆኖም፤ የምናገረው ትክክለኛ መስሎ የታየኝንና ከልቤ የማምንበትን መሆኑ እንዲታወቅልኝ አስቀድሜ እለምናለሁ። የግርማዊነትዎ ወደ ዤኔቭ መሔድና በዚያ ለሚገኘው የመንግሥታት ማህበር ሸንጎ ንግግር ማድረግ እጅግ አስፈላጊ ብቻ ሳይሆን፤ እጅግ ጠቃሚ እንደሚሆን ግልጽ ሆኖ ይታየኛል።

ጠቃሚ ነው የምለውም፤ የመንግሥታቱ ማህበር በግፈኛ መንግሥት የተጠቃውን የኢትዮጵያን ነፃነት ለማዳን፤

- በብዙ ሺህ የሚቆጠር ሠራዊት ያሰልፍልዎታል፣
- የአየር ኃይሉንና የምድር ጦሩን ያዘጋጅልዎታል፤

ብዬ አይደለም። በእኔ በትንሹ አገልጋይዎ አስተያየት፤ የመንግሥታት ማህበር በጦር በኩል አንዳች እርዳታ ያቀርብልዎታል ብዬ ተስፋ አላደርግም። ነገር ግን፤ ግርማዊነትዎ ዤኔቭ ላይ የሚያደርጉት ንግግር ጠቃሚ ይሆናል የምለው፤ የተመሠረተበትን ዓላማ ስቶ፤ ለኮሎኒያሊስቶችና ለጥጋበኞች መሣሪያ የሆነውን የመንግሥታት ማህበር፤ ለዓለም ሕዝብ ያጋልጡታል ብዬ ነው። የድሆች መንግሥታት እየተጠቁ፤ የኀቶች መንግሥታት እንዲጠቀሙ የሚሠራ ማህበር፤ በግርማዊነትዎ ንግግር ምናልባትም ለሕይወቱ ፍጻሜ ያበቃው ይሆናል የሚልም ተስፋ ያድርብኛል። በግርማዊነትዎ አቤቱታ የሚገኘው ጥቅም ይህ ብቻ አይደለም። ታላላቆች የተባሉትንም መንግሥታት፤ በተለይ የፈረንሣዮችን ክዳት፤ የእንግሊዞችን ማህል ቤት መቃተት፤ የአሜሪካኖችን ግዴለሽነት ለዓለም ሕዝብ አጋልጦ ትዝብት ላይ ይጥላቸው ይሆናል ብዬ አስባለሁ። እዚህ ላይ ግርማዊነትዎ ቢፈቅድልኝ፤ አንድ ዤኔቭ ላይ የደረሰ አጭር ታሪክ ለመጥቀስ እፈልጋለሁ። ይኸውም፤ በዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር የግርማዊነትዎ ባለሙሉ ሥልጣን መላክተኛ የነበሩት ፊታውራሪ ተክለ ሐዋርያት፤ ባለፈው ጥቅምት ወር ሥራቸውን ለቅቀው ወደ አዲስ አበባ ከመመለሳቸው በፊት፤ ለጉባኤው ያሰሙት አጭር ንግግር ነው። ይህንንም ቃል በስዊስ ራዲዮ አዳምጦ ቃርሞ የላከልኝ ግርማዊነትዎ ፈረንሣይ አገር ያስተማሩት ትንሹ ወንድሜ አክሊሉ ሀብተወልድ ነው። በስዊዝ ራዲዮ የተነገረው፤ ከፊታውራሪ ተክለ ሐዋርያት ንግግር ውስጥ ፍሬ ነገሩ የሚከተለው ነበር።

<u>የመንግሥታት መልዕክተኞች ፤</u>

> « ... እኔ ተመራምሬ እንደ ደረስኩበት፤ የመንግሥታት ማህበር ተግባሩን የሚያከናውንበት ሁለት ዓይነት ምሥጢራዊ ሕጎች አሉት። እነዚህም ሕጎች የአጥቂና - የተጠቂ ተብለው የሚሠየሙ ናቸው። በእነዚህ ሕጎች መሠረት፤ አጥቂው እንደፈለገው እንዲያጠቃ፤ ተጠቂውም እንደፈረደበት ግፉን እንዲቀበል፤ የመንግሥታት ማህበር መብቱን በየመልኩ ይጠብቅለታል። በዛሬው ሰዓት ያለው የመንግሥታት ማህበር አሠራር ይህ ነው። ስለዚህም፤ አገሬ ኢትዮጵያ የተፈረደባትን ግፍ እየተቀበለች በመሰቃየት ላይ ስለሆነች፤ እኔም አገልጋይዋ ከሥቃይዋ ለመካፈል ይህን የግፍ ፍርድ የምታካሂዱበትን ሸንጐአችሁን ለቅቄላችሁ እሔዳለሁ። የማቀርብላችሁ የስንብት ሰላምታ በልማድ እንደሚሠራበት "በደህና ይግጠመን አይደለም" ለምንጊዜውም " ለመገናኘት አያብቃን " የሚል ነው።

ይህንን አጭር ታሪክ ለመጥቀስ የፈለግኩት፤ በአሁኑ ሰዓት ያለው የመንግሥታት ማህበር አሠራር፤ ፊታውራሪ ተክለ ሐዋርያት በገለጡት አኳኋን መሆኑን ተገንዝቤ በመገረም ነው።

ጃንሆይ !

በመጨረሻ ልናገር የምፈልገው፣ በዛሬው ሰዓት በአገራችንም ሆነ በውጭው ዓለም የሚወራው ኢትዮጵያ ድል ሆናለች እየተባለ ነው። ኢትዮጵያ ድል አልሆነችም። ገና ጦርነቱ ይቀጥላል። ለጊዜው ግን ሕዝብም በዓለም ሕግ በተከለከለ በአውሮፕላን በሚረጭ መርዝና የጋዝ ጢስ ስለአለቀ፣ ሌላ ዘዴ እስከሚገኝ ድረስ፣ የመከላከያውን ጦርነት መቀጠል አልተቻለም። ጥንቱንም ቢሆን ግርማዊነትዎ ጦርነትን አልፈለገም። ለጦርነትም አልተዘጋጀም። ጦርነትን ፈልገው የመጡት፣ በዓለም የታወቁት ሕገወጦችና ዕብሪተኞቹ ናቸው። ይህንንም የዓለም መንግሥታት ማህበር ደህና አድርጐ ማወቅ ብቻ ሳይሆን አጥፊው ማን እንደሆነም ለይቶ ተናግሯል። ነገር ግን፣ የኢትዮጵያንና የሌላውንም የዓለም ሕዝብ ከፍ ያለ ኃዘን ላይ የጣለው፣ ጦርነቱን የጀመረው ፋሽስት መሆኑን የመንግሥታት ማህበር መርምሮ ማረጋገጥ ከቻለ በኋላ፣ በማህበሩ ሕግ መሠረት፣ በተለይ ስለ ኢኮኖሚው ዕገዳ ፍርዱን በትክክል ለማስፈጸም ሳይፈልግ በመቅረቱ ነው። ለዚህ በደል ሲጠየቅ፣ ምን መልስ እንደሚሰጥበት፣ ምን ምክንያት እንደሚያቀርብበት፣ ግርማዊነትዎ በገኔቭ ይመለከቱት ይሆናል ብዬ ጽኑ ተስፋ አደርጋለሁ። ልዑል ራስ ካሣ እንዳሉት፣ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማዳንና የሕዝብዎን ሰላም ለመጠበቅ የሚችሉት፣ በእግዚአብሔር ቸርነት መጀመሪያ እርስዎ ደህና ሆነው ሲገኙ ነው። በሚያደርጉት ጥረት ሁሉ፣ አምላክዎ እንደማይለይዎና ሕዝብዎም ከእርስዎ ጋር መሆኑን እንዲያውቁት እያልኩ ልመናዬን አቀርባለሁ … »

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ከልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣ ከብላቴን ጌታ ሕሩይ ወልደ ሥላሴና ከአቶ መኰንን ሀብተ ወልድ የቀረበውን አስተያየት ንጉሠ ነገሥቱ ካደመጡ በኋላ፣ የሚከተለውን ተናግረው ውሳኔ ሰጡ።

« … ሁላችሁም ለአገራችን ነፃነት የምትሰቃዩና መሥዋዕት ለመሆንም ወደ ኋላ የማትሉ ናችሁ። በዚህም አኳኋን የምታቀርቡልን ምክር ሁሉ እውነተኛውንና በእግዚአብሔርም ሆነ በሰው ዘንድ የሚከበረውን ስለሆነ፣ ሙሉ ዕምነት እናሳድርበታለን።

- ራስ ካሣ በተናገሩቸው ብዙዎች በሆኑት ፍሬ ነገሮች ውስጥ፣ ገኔቭ ሄደን የምናቀርበው አቤቱታ አድማጭ ካጣ፣ በአንደኛው ጠረፍ በኩል ወደ አገራችን ተሻግረን የአርበኝነት ተግባር ለመፈጸም ይቻላል ያልከው፣ ከሐሳባችን ጋር የተገጣጠመ ሆኖ ስላገኘነው ደስ ብሎናል።

- ሕሩይ በተናገርከው ውስጥ፣ ለነፃነት መዋጋት በጦር ሜዳ ብቻ ሳይሆን፣ በፖለቲካውም፣ በፕሮፓጋንዳውም በኩል መሆን አለበት ያልከው፣ የምንስማማበት መልካም አስተያየት ነው።

- መኰንን ሀብተወልድ የተናገርከው ከጠበቅነው በላይ ነው። ገኔቭ ሄደን አቤቱታችንን የምናቀርብለት የመንግሥታት ማህበር፣ ጠላታችንን ከአገራችን ለማስወጣት በጦር ሠራዊት ሆነ በመሣሪያ ምንም ዓይነት እርዳታ እንደማይሰጠን ተስፋህን ቆርጠሀል። እንዳልከው፣ እኛም ይህን ያህል እናገኛለን ብለን ተስፋ አላሳደርንም። ተክለ ሐዋርያት በገኔቭ በመጨረሻ ቀኑ ስለተናገረው የጠቀስከው ማለፊያ ነው። መቼም እሱ

በጠባዩ ጥሩ ነገር ሲሠራ አይናገርም። እኛም የሰማነው እሱ ነግሮን አይደለም። የሚያሳዝነው ይህን የመሰለ ንግግር አድርጎ ከአዳራሹ ሲወጣ፤ ከጓደኞቹ የመንግሥታት እንደራሴዎች መካከል ያመሰገነውም ያደነቀውም አለመኖሩ ነው። ከዚህ ሌላ በተናገርከው ውስጥ፤ ፈረንሣይ በሙሴ ላቫል መንግሥት ጉዳት ቢያደርስብንም፤ እንግሊዝም ፊት ለፊት ተጋፍጦ ጠቃሚ እርዳታ ባይሰጠንም፤ ከአሜሪካም የጠበቅነውን ባናገኝም፤ የወደፊቷ ኢትዮጵያን በማሰብ፤ ተስፋ መቁረጥ የለብንም። እነዚህ አገሮች ሁሉ ለዛሬው ባይሆኑን ነገ ተመልሰው አገራችንን ሊጠቅሙ ይችሉ ይሆናል ብለን ማሰብ ይሻለናል። ዛሬ ያለንበት ሁኔታ፤ በሞትና በሕይወት መካከል የሚያጣጥር ነው። የጦር መሣሪያ ባጠረን ጊዜ፤ ሠራዊታችንም ተዳክሞ በተበታተነበት ሰዓት፤ ጥቂት ተዋጊዎች ይዘን ጠላትን እንመከታለን ብለን ብንነሣ፤ በመጀመሪያ ሰላማዊውን የአዲስ አበባን ሕዝብ እናስጨርሳለን። እኛም እናልቃለን። ስለዚህ፤ መንግሥታችን ወደ ጐሬ (ኢሉባቦር) ተዛውሮ በቢትወደድ ወልደጻድቅ ጉሹ እየተመራ እንዲቆይና፤ እኛም አቤቱታችንን ለዓለም መንግሥታት ማህበር ለማቅረብ ወደ ዤኔቭ እንድንሄድ ያቀረባችሁልንን ሐሳብ ተቀብለናል። በዚህ መሠረት፤ ቤተመንግሥታችንን ለቅቀን እንደወጣን፤ ጠላት የአዲስ አበባን ሕዝብ በመርዝና በጋዝ እንዳይፈጀው፤ ከተማው "ነፃ ከተማ" ተብሎ ይታወጅ።*

ንጉሠ ነገሥቱ ይህን ተናግረው ስብሰባውን ሲዘጉ፤ ጊዜው ውድቅት ሌሊት ለመሆን ተቃርቦ ነበር። በማግስቱ ዓርብ ሚያዝያ 23 ሙሉውን ቀን በቤተመንግሥቱ የጉዞው ዝግጅት ሲጠናቀቅ ከቆየ በኋላ፤ ለቅዳሜ ሚያዝያ 24 አጥቢያ ሌሊቱን፤ ንጉሠ ነገሥቱ ንጉሣውያን ቤተሰቦቻቸውንና አንዳንድ ታላላቅ ሰዎችን አስከትለው በልዩ ባቡር ከአዲስ አበባ ወደ ጂቡቲ አመሩ።

አቶ መኰንን ሀብተወልድ በያዙት አጭር ማስታወሻ ላይ እንደ ጠቀሱት፤ ይህ ወሳኝ በሆነው ለመጨረሻ ጊዜ በቤተመንግሥቱ በተደረገው ስብሰባ ላይ ተካፋይ የሆኑት ሰዎች፤ ቁጥራቸው ከአሥራ አምስት አይበልጥም ነበር ብለዋል። ከዚህ ቀደም ሲል በተደረገው ትልቁ ስብሰባ ላይ ግን፤ አርባ ሦስት (43) ሰዎች ተካፋይ እንደነበሩ ታውቋል።

* የፋሽስት ጦር አዲስ አበባ ከተቃረበ በኋላ፤ ምን እርምጃ መውሰድ እንደሚያስፈልግ በቤተመንግሥቱ በንጉሠ ነገሥቱ ሊቀመንበርነት ታላቅ ስብሰባ ተደርጎ፤ የተሰጠውን ውሣኔ ቃለ ጉባኤ የያዙት አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ በዚያን ጊዜ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ ናቸው።

# ምዕራፍ ፲፪

## ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዤኔቭ

የአሥራ ስድስተኛው የመንግሥታት ማህበር ጠቅላላ ጉባኤ በሚካሄድበት ወቅት፤ እ.ኤ.አ ሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለአምሳ ሁለት (52) አባል መንግሥታት እንደራሴዎች ንግግር የሚያደርጉበት ዕለት እንዲሆን አስቀድሞ ተወስኖ ነበር።

በዚህ ቀን ጉባኤው የሚጀመረው ከእኩለ ቀን በኋላ በአሥራ አንድ ሰዓት ስለነበረ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከአንድ ሰዓት በፊት የክብር ተከታዮቻቸውን አስከትለው ከሊግ ኦፍ ኔሽን መሰብሰቢያ አዳራሽ መግቢያ በር ላይ ሲደርሱ፤ በወጉ ለአንድ አገር መሪ የሚደረገው የፕሮቶኮል አቀባበል አልተደረገላቸውም። በዚህ የታሪክ መጽሐፍ ውስጥ በልዩ ልዩ ጉዳዮች ላይ ተዘርዝሮ እንደ ተገለጸው፤ የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ የሆነው ፈረንሣዩ ዮሴፍ አቬኖል፤ (Joseph Avenol) የጣልያኑ ዲክታተር የቤኒቶ ሙሶሊኒ የፋሽስት መንግሥት ዋና ደጋፊ በመሆኑ፤ በኢትዮጵያ ጉዳይ የሚያመች መንገድ በአጋጠመው ቁጥር ብዙ ተንኮል ሲፈጽም የቆየ ነው። አሁንም የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በመንግሥታት ማህበር ጉባኤ ላይ ለመገኘት ብዙ ሺህ ማይልስ ተጉዘው ከሊግ ኦፍ ኔሽን አዳራሽ ሲደርሱ፤ ዮሴፍ አቬኖል በዋናው በር ላይ ቀይ ምንጣፍ ዘርግቶ የፕሮቶኮል አቀባበል ያላደረገላቸው፤ ወዳጆቹ የሆኑትን ፋሽስቶቹን ለማስደሰት መሆኑ በግልጽ የታወቀ ነበር። በዚህ ጊዜ የንጉሠ ነገሥቱ የፖለቲካ ጉዳይ አማካሪና የመልዕክተኞች አባል የሆኑት፤ **" ሚትር ሎሬንሶ ታዕዛዝ "** የተፈጸመው የፕሮቶኮል ጉድለት ምክንያቱ ለምን እንደሆነ ዋናውን ጸሐፊ ሲጠይቁ፤ « ... **ንጉሠ ነገሥቱ የመጡት የኢትዮጵያ መልዕክተኞች መሪ ሆነው የአገራቸውን ጉዳይ ለጠቅላላው ጉባኤ ለማመልከት እንጂ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን እንግዳ ሆነው ንግግር እንዲያደርጉ የተጋበዙ ባለመሆናቸው ነው ...** » የሚል መልስ ተሰጣቸው። ሎሬንሶ፤ የተሰጠው ምክንያት አጥጋቢ ሆኖ አላገኙትም። በፓሪስ ከኤሊዜ (Elysée) ቤተመንግሥትና ከሎንደን ከባኪንግሃም ፓላስ የፕሮቶኮል ሰዎች ጋር በስልክ ሐሳብ ለሐሳብ ሲለዋወጡ፤ « ... **በመንግሥታት ማህበር ጠቅላላ ጉባኤ ላይ ተካፋይ ለመሆን የአንድ አባል አገር መሪ ራሱ መልዕክተኞቹን እየመራ ሲመጣ፤ ምንም እንኳ የሊጉ የክብር እንግዳ ሆኖ የተጋበዘ ባይሆንም፤ ቢያንስ በመጀመሪያው ዕለት ከስብሰባው አዳራሽ ዋና መግቢያ ላይ ተገኝቶ ዋናው ጸሐፊ የክብር አቀባበል ማድረግ ይገባው ነበር ...** » የሚል አስተያየት አገኙ። በዚህ መሠረት፤ ሎሬንሶ ታዕዛዝ ከሕግ አማካሪው ከፕሮፌሰር ዤዤ (JEŽE) ጋር ሆነው፤

1ኛ/ በዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ዋና መልዕክተኛ የሆኑት ብላቴን ጌታ ወልደማርያም፤ በፕሮቶክል ረገድ ዋናው ጸሐፊ በንጉሠ ነገሥቱ ላይ የፈጸመውን በደል ለየመንግሥታቱ እንደራሴዎች እንዲገልጹ፤

2ኛ/ ሎሬንሶ ታእዛዝ በፖለቲካ ጉዳይ አማካሪነታቸው የፕሬስ ጉባኤ አድርገው፣ የዮሴፍ አቬኖልን አድራጎት ለጋዜጠኞች እንዲያስረዱ፣ የንጉሠ ነገሥቱን ፈቃድ ጠየቁ።

ጃንሆይም በበኩላቸው፣ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉን፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራቸውን ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴን፣ ልዩ ጸሐፊያቸውን አቶ ወልደ ጊዮርጊስ ወልደ ዮሐንስን ይዘው፣ ከሁለቱ የፖለቲካና የሕግ አማካሪዎች ከሆኑት ከሜትር ሎሬንሶና ከፕሮፌሰር ዤዝ የቀረበላቸውን ሐሳብ ካጠኑ በኋላ፣

« ... እኛ እዚህ ዤኔቭ ድረስ የመጣነው፣ በአገራችን ነጻነትና በሕዝባችን ላይ የሚፈጸመውን ግፍ አመልክተን ትክክለኛ ፍርድ እናገኛለን ብለን ነው። በአሁኑ ጊዜ አገራችን በፋሽስት ጦር ተይዛ፣ ሕዝባችን በጠላት እጅ በሚፈጅበት ሰዓት፣ በዤኔቭ ያለው የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ በፕሮቶኮል አቀባበል በድሎናል ብለን በአደባባይ መናገር፣ ከክብራችን ጋር የሚስማማ ሆኖ አላገኘነውም። የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ ጨዋ ሰው ቢሆን ኖሮ፣ እኛን የጎዳን መስሎት ይህን የረከሰ ተግባር ሲፈጽም ባልተገኘ ነበር። በዚህ ጉዳይ እኛ እንደ እሱ ሆነን መታየት የለብንም። አቶ ሎሬንሶና ፕሮፌሰር ዤዝ ያቀረባችሁልን ሐሳብ ለአገራችንና ለንጉሠ ነገሥቷ ክብር በመቆርቆር መሆኑን በሚገባ ተረድተነዋል። ነገር ግን፣ ያቀረባችሁት ሐሳብ ለጊዜው ቢቀር ይሻላል የምንለው፣ በዚህ በዓለም መንግሥታት ጉባኤ ላይ የክብራችንን ጉዳይ አገራችን ከደረሰባት መከራ ጋር አጣምረን መናገሩ፣ ሌላ ግምት ላይ እንዳይጥለን በመሥጋት መሆኑን እንድታውቁት እንጠይቃችኋለን ... » የሚል ውሳኔ ሰጡ። *

ፕሮፌሰር ጋስቶን ዤዝ በማስታወሻው ላይ እንደ ገለጸው፣ « ... በንጉሡ ውሳኔ ሎሬንሶና እኔ ቅር ተሰኝተን ነበር። በተለይ ሎሬንሶ በጣም ተበሳጭቶ ንጉሡ የእነዚህን የሁለት ሽማግሌዎች፣ የራስ ካሣንና የብላታ ኅሩይን ምክር እያዳመጡ ወደፊት መግፋት አልቻልንም እስከ ማለት ደርሶ ነበር። ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣ ሁለታችንም (ሎሬንሶና እኔ) ነገሩን ስናየው፣ የሁለቱ ሽማግሌዎች ምክር የሚነቀፍ አልነበረም። እኛ እንዳሰብነው፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኛ በጠቅላላው ጉባኤ ላይ ስለ ፕሮቶኮል በደል አቬኖልን በመውቀስ ንግግር አድርጎ ቢሆን ኖሮ ምንም ዓይነት ጥቅም አይገኝም ነበር ... » ብሏል።

እ.ኤ.አ ማክሰኞ ሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት፣ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉን የበጌምድርና የሰላሌ ገዥ፣ ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደ ሥላሴን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣ ደጃዝማች ነሲቡ ዘ-አማኔልን የሐረር እንደራሴ፣ አቶ ወልደ ጊዮርጊስ ወልደ ዮሐንስን (ኋላ ጸሐፊ ትዕዛዝ) የንጉሠ ነገሥቱ ልዩ ጸሐፊ፣ አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝን (ኋላ ብላቴን ጌታ) የንጉሠ ነገሥቱ የፖለቲካ አማካሪ፣ አቶ ኤፍሬም ተወልደ መድህንን (ኋላ ብላቴን ጌታ) የንጉሠ ነገሥቱ ተዘዋዋሪ መልዕክተኛ፣ አስከትለው ከሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና መግቢያ በር ሲደርሱ፣ የኮንፌራንስ አስተናባሪዎች ተቀብለዋቸው፣ በስብሰባው አዳራሽ ውስጥ ለኢትዮጵያ መልዕክተኞች በተመደበው ገበታ ላይ ወንበራቸውን ያዙ።

---

* ከፕሮፌሰር ዤዝ ሪፖርት የተገኘ የአክሊሉ ሀብተወልድ ማህደር

ቀደም ሲል ተዘጋጅቶ በነበረው ፕሮግራም እንደ ተገለጸው፣ በዚህ በሰኔ 30 ቀን የአሥራ ስድስተኛው የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ሥራውን ሲጀምር፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የመጀመሪያው ተናጋሪ እንዲሆኑ አልተደረገም። ለዚህም፣ የኮንፌራንሱ ፕሮግራም መሪ ሁለት ዋና ዋና አድርጎ የሚቆጥራቸውን ምክንያቶች ደርድሯል። የመጀመሪያው ምክንያት፣ የጉባኤው ሊቀመንበር የነበረው የቼኮስሎቫኪያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሙሴ ኤድቫርድ ቤነስ (Edvard Benes) የአገሩ ፕሬዚዳንት ለመሆን በእስቸኳይ ተጠርቶ ስለሄደ፣ በእሱ ቦታ የሚተካውን የቤልጊኩን ጠቅላይ ሚኒስትር የማስመረጫ ሥነ ሥርዓት ለማድረግ ሲሆን፣ ሁለተኛው ምክንያት ደግሞ፣ የዱቼ ሙሶሊኒ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ኮንት ጋሌአሶ ቺያኖ (Galeasso Ciano) ንጉሥ ኃይለ ሥላሴን የኢትዮጵያ ሕዝብ አስገድዶ ከአገር ያስወጣቸው ስለሆነ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ላይ ንግግር ማድረግ የለባቸውም በማለት፣ በሰፊው የጻፈው እጅግ አሳዛኝና ርካሽ የሆነ ዶክመንት ለመልዕክተኞቹ በቅድሚያ እንዲነበብ አስፈላጊ ነው ብሎ ዋናው ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል በማዘጋጀቱ ነበር።

የኢንተርናሽናል ስብሰባን ሥነ ሥርዓት የሚያውቅ ሁሉ እንደሚረዳው፣ ለጉባኤው ሊቀመንበርነት የሚደረገው ምርጫ ከሁሉም ቅድሚያ እንዲሰጠው አስፈላጊነቱ ባያከራክርም፣ የሕገ ወጡ የፋሽስት መንግሥት ፕሮፓጋንዳ፣ ከኢትዮጵያ መሪ ንግግር በፊት እንዲቀረብ መደረጉ እጅግ የሚያሳዝን ነው። ንጉሠ ነገሥቱ ጄኔቭ መጥተው በአሥራ ስድስተኛው ጠቅላላ ጉባኤ ላይ ንግግር ለማድረግ ከአንድ ወር በፊት በጠየቁት መሠረት፣ ለሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም ፕሮግራም የተያዘላቸው ስለሆነ፣ ከዚህ ጊዜ አንድ ቀን በፊት ሰኔ 29 ቀን ከፋሽስት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የተላከው የዘለፋና የፕሮፓጋንዳ መልዕክት፣ እንዴት ከኢትዮጵያ መሪ ንግግር ቅድሚያ ይሰጠዋል? ..... የመንግሥታት ማህበር ድርጅት የሚካሄደው የፋሽስት ደጋፊዎች በሆኑ ሰዎች ስለሆነና፣ ተግባሩንም የሚያከናውነው ለኮሎኒያሊስቶቹ መንግሥታት ጥቅም እንጂ፣ የድሆችን አገሮች መብት ለማስከበር ባለመሆኑ፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የመናገሪያ ተራቸው ደርሶ ሊቀመንበሩ እስከሚጠራቸው ድረስ፣ በትዕግሥት ከመጠበቅ በስተቀር ምንም ዓይነት የቅሬታ መንፈስ አላሳዩም።

የፋሽስት መንግሥት ኢትዮጵያን ጥፋተኛ አድርጉ በመክሰስ ያቀረበው የዘለፋና የቅጥፈት ደብዳቤ ተገቢ ባልሆነ ሥርዓት ለጉባኤው ተካፋዮች ከተነበበ በኋላ፣ አዲሱ ፕሬዚዳንት የቤልጊክ ጠቅላይ ሚኒስትር « ... አሁን የኢትዮጵያ መልዕክተኞች መሪ የሆኑት ንጉሥ ኃይለሥላሴ እንዲናገሩ መድረኩን እሰጣቸዋለሁ ... » ሲል የሊቀመንበርነት ደወሉን አሰማ። በዚህ ጊዜ፣ በኢትዮጵያ የባህል ልብስ ላይ ጥቁር ካባ የደረቡት ንጉሠ ነገሥት ከወንበራቸው ተነሥተው፣ ግርማ ሞገስና እርጋታ በተመላበት አረማመድ ከመናገሪያው ሰገነት ላይ ሲደርሱ፣ በስብሰባው አዳራሽ ፎቅ ግራና ቀኝ ባሉት ጋለሪዎች ላይ ተሰግስገው የሚጠባበቁት የፋሽስት ወሮበሎች፣ በሚያሰሙት ከፍ ያለ የብልግና ጩኸትና ፉጨት፣ የስብሰባውን አዳራሽ ፀጥታ አደበላለቁት። ንጉሠ ነገሥቱ ግን ከቆሙበት የመናገሪያ ሰገነት ላይ ምንም ዓይነት እንቅስቃሴ ሳያደርጉ ቀጥ ብለው በመቆም ፀጥታው እስኪሰፍን ድረስ በሚጠባበቁበት ጊዜ፣ ከመንግሥታት እንደራሴዎች መካከል አንዱ፣ የሩማንያው የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሙሴ ኒኮላ ቲቱሌስኮ (Nicolas Titulesco) እጅግ በተበሳጨ መንፈስ ከወንበሩ ብድግ ብሎ፣ « ... እነዚህን ባለጌዎች የሆኑትን አውሬዎች ለፍርድ ስትል አስወጣልን ... » ሲል ሊቀመንበሩን ጠየቀ።

ከሩማንያው መልዕክተኛ ጥያቄ በኋላ፣ በጉባኤው ላይ ተካፋይ ከሆኑት መካከል፣ በፒየር ላቫል ቦታ የተተካው የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር ሌዎን ብሉምና (Leon Blum) የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን (Antony Eden) በአዳራሹ ውስጥ በታየው የፋሽስቶች ብልግና ከፍተኛ ቅሬታቸውን ስለአሰሙ፣ ፖሊሶች ተጠርተው ወሮበሎቹ እየተገፈተሩ እንዲወጡ ተደረገ። እዚህ ላይ፣ በመንግሥታት ማህበር ትልቅ ስብሰባ ላይ ይህን የመሰለው አሳፋሪ ሁኔታ እንዴት ሊፈጠር እንደቻለ ምርምር ቢደረግ፣ የዱቼ ወገን የሆነው የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ ተባባሪ መሆኑን ለማመን አያዳግትም። በደንቡ መሠረት፣ በዋናው ስብሰባ አዳራሽ ግራና ቀኝ የሚገኙት ጋለሪዎች፣ ታላላቅ ጉባኤዎች በሚካሄዱበት ጊዜ፣ ዲፕሎማቶች፣ የፓርላማ አባሎችና ታላላቅ ሰዎች እየተጋበዙ፣ የኮንፈራንሱን ሥራ የሚከታተሉበት እንጂ፣ የባለጌዎች መጨፈሪያ እንዲሆኑ የተዘጋጁ አይደሉም። ስለዚህም፣ በዚህ ዕለት ለፋሽስቶቹ ወሮበሎች የመግቢያ ፈቃድ ሰጥቶ በጋለሪዎቹ ላይ ቦታ እንዲይዙ ያደረጋቸው የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ ቢሮ ስለሆነ፣ የኢትዮጵያን ንጉሠ ነገሥት እናዋርዳለን በሚል ርካሽ መንፈስ የተፈጸመ ድርጊት ለመሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም።

ፖሊሶች ተጠርተው ፋሽስቶቹን ካስወጡና በስብሰባው አዳራሽ ላይ ፀጥታው ከሰፈነ በኋላ፣ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ለአምሳ ሁለት መንግሥታት እንደራሴዎች ያሰሙት ንግግር፣ ጨካኙ የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ የፈጸመውን ግፍ ብቻ ሳይሆን፣ በዚህ ጉዳይ የመንግሥታት ማህበርም የሚጠበቅበትን ትክክለኛ ፍርድ ካልሰጠ፣ እግዚአብሔርና ታሪክ ሥራውን ሊያስታውሱት እንደሚኖሩ ትንቢታቸውን ጭምር ነበር። በሊግ ኦፍ ኔሽን ታሪክ ላይ ለዘለዓለሙ ተመዝግባ በምትኖረው በዚች ማክሰኞ ሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ያደረጉት ንግግር፣ በየመጻሕፍቱና በልዩ ልዩ የታሪክ ሰነዶች በሙሉ ሲታተሙ የኖሩ መሆናቸው የታወቀ ነው። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ግን፣ በዛሬው ድርሰቱ ይህን የገኔቩን ታሪካዊ ንግግር ለአንባቢዎቹ የሚያቀርበው፣ የተደረገውን ዲስኩር ቃል በቃል በማተም ሳይሆን፣ በተገለጹት ጽሑፎች ውስጥ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልዕክቶች ዋና ዋናዎቹ የትኞቹ እንደነበሩ በየጉዳዩ እየለየ በማብራራት ነው። ደራሲው ለረዥም ዘመናት ባሳለፈው የጋዜጠኝነት ሞያው፣ የገኔቩን ታሪካዊ ዲስኩር መሠረታዊ ሐሳብ ሳይለቅ፣ አቀራረቡንና አገላለጹን የተለየ መልክ ለመስጠት ጥረት ያደረገበት ምክንያት፣ የዛሬውም ሆነ የነገው ትውልድ በቀላሉ አንብቦ ለመረዳት እንዲችል በማሰብ መሆኑን እንዲታወቅለት ይፈልጋል።



ቀ.ኃ.ሥ እና መልዕክተኞቻቸው ወደ ሊግ ኦፍ ኔሽን አዳራሽ ሲያመሩ፤
(June 30/36)



የሊግ ኦፍ ኔሽን የስብሰባ አዳራሽ፤